እነዚሁንም ዕቃቸውንም የሚጭኑበት ቢያጡና እጅግ ቢቸገሩ የተገ
ዘብ መውደድ ይመስልብኛል ብለው የኪራይ በቅሎ ለተተው ከነ
ዕቃቸው ሒዱ ብለው ሰደዱአቸው ። እነዚያ ጣልያኖች ግን ከውሃው
ጥፋት የተነሣ ከባሻ ባሎቃ (የጥቁር ሹማምንት) ጋር ሊዋጉ ደርሰው
ነበር ። እንደነዚያ ከፋት ቢሆን አንድ ወሬ ነጋሪ ባልተረፈም ነበር ።
የምኒልክን ደግነት ሲቻለው የሚገተው ንጉሥ በኢትዮጵያ መኖሩን
የሰማ አውሮፓ ምን ይል ይሆን እንጃለን ። እስከዛሬ ድረስ የተደረገ
ውን የጦር ነገር ይኸውና ላኩሁብዎ[1]

እንዲሁም እኚሁ ግራዝማች ዮሴፍ ፡

.. ይህ ሁሉ ሲሆን ከመቀሌ ተነሥተን ያል (ፊሪሰማይ) እስከን ደርስ ድረስ ኢጣልያኖች የእርቅ ወሬ ሲያወሩ ሰነበቱ ። የነዚያ ሹማምንቶችና ፊልተር የሚባለው ነጋዴ ከበፊር ሲመላለሱ ነበር ። ጃንሆይም ተንከላቸውን በውቀውባቸው ቶሎ ቶሎ ገሥግሠን ግታ ላይ ሰፈርን ። ኢጣልያኖቹም ከእዲግራት ወጥተው እዲጋ ሐሙስ ላይ ሰፍረው ነበር ። የኛም ጦር ወጥቶ አጠገባቸው ሰፈረ ። እነዚያም የጦሩን ብዛት ባዩ ጊዜ ለመድፍ የሚያመች ሰፍራ ፈልገው ካብ ይከቡ ጀመሩ ።

ብለው ሲጽፉ ፡ ፊልተር ከኢጣልያ ጦር ጠቅላይ አዛዥ ሰላም ፈላጊ መስሎ የመዘጋጃ ጊዜ ለማስገኘት ተልኮ እስፈራቸው የመጣበትን የማታለል ሰበብ ዐፄ ምኒልክ እንደ ተረዱት ያስታውቃል ። በዚህም ንጉሠ ነገሥቱ የጦር ድርጅቱን ሥራ ከማከናወናቸውም በላይ ወሬና መረጃ መጥቀሙን ተረድተው የየጊዜውን ሁኔታና የጠላትንም አሳብ ያስመረምሩ ነበር ማለት ነው ። በተረፈ በሌላ ረገድ የፊልተርና የግራዝማች ዮሴፍ አጻጻፍ በመሠረቱ አንድ ነው ። ግራዝማች ዮሴፍ ባጻጻፋቸው ንጉሠ ነገሥታቸውን የማድነቅና የማስደነቅ ፡ የማከበርና የማስከበር ነገር ሲያሳዩ ፡ ጣልያኑም የራስ መኰንን የቅን ወዳጅነት መሳሪያ አድርጎ የኢትዮጵያን መንግሥት በዕርቅ ስም እያታለለ ከኢጣልያ አገር የሚመጣው የእርዳታ ጦር እንደደርሰ እስኪገባ ድረስ የ35 ቀን ጊዜ እንዲያሰጥ ከጀኔራል ባራቲዬሪ ተልኮ የመጣበትን መልእክት ፈጽሞ ከተመለሰ በኋላ ፡ ባለፈው ባነበብነው ራፖር ውስጥ የርሱን ወገኖች በአጻጻፉ ለመደገፍና ለሚሠሩት ሁሉ ደንበኛ መንገድ ለመስጠት እንደ ሞከረ ያሳያል ። ቢሆንም ነገሩን በጠቅላላው ስንመለከት ያፄ ምኒልክ ዋና አሳብ ፡ "በወሃ ጥም ሊያልቅ የነበረውን የጦር ሠራዊት ከሞት አትርፎ ዕቃውን የሚጭንበት አጋሰስ አዝጋጅ ሰጥቼ ስለከለት የአውሮፓ ሕዝብ ይፈርደኛል ፤ ጠላቴንም ይወቅሰልኛል ፡ እርሱም ይኸን ሁሉ አመዛዝኖ ሕዝቡን ሳያስጨርስ በእርቅ አገሬን ለቆ ይሔዳል ፤ እምቢ ቢልም የተከተለኝ የጦር ሠራዊት

1 ፓሪስ ቤተ መጻሕፍት ከምንገኘው ዘዳቶ ዶሲዬ የተገኘ ።



የርሱን ጦር ለመምታትና ለማሸነፍ በማናቸውም ሥፍራ በማናቸውም ጊዜ አይሰንፍም የሚል ነው ።

በዚህ የተደራረበ አሳብና ተስፋ ላይ በመመሥረት ለጠላት የእርቅና የሰላም መንገድ ማሳየታቸውን ሳይለቁ ደግሞ የፍርሃት መስሎት የልብ ልብ እንዳይበታው ፡ "የክርስቲያን ንጉሥ ነኝ እንጂ ፡ የአሕዛብ ንጉሥ አይደለሁም አሁንም ክርስቲያኖች በከንቱ እይለቁ ሰዎችህን ልከህ አስወስድ ፤ አገር ሊፈልግ የመጣ ጦር ጉድባ ውስጥ አይገባምና ትዋጋም እንደሆን እንድንት ተሰብስበዓችሁ ቆዩኝ" ብለው ለዋናው ጠቅላይ አዛዥ ለጀኔራል ባራቲዬሪ ላኩበት ። እርሱ ግን ፡ ርኅራኄያቸውንም ጉልበታቸውንም ቢሆን የፖለቲካና የእርቅ መንገዳቸውንም ከምንም አልቆጠረውም ። የጠበቀው የእርዳታ ጦር ከጥር ወር ጀምሮ ከኢጣልያ በመርከብ እየተጋዘ ሲደርስለት ፡ በወሃ ጥም ሊሞት የነበረው የመቀሌው ጦር በነጻ ተለቆ በእጁ ሲገባ የዕርቁን ነገር በጭራሽ ትቶ ለዋናው ለዓድዋ ጦርነት ይዘጋጅ ጀመር ።

ቢሆንም ፡ የኢጣልያ ጦር ያዳግባብ የሰው አገር ወሰን ጥሶ የወራሪነት ሥራ በሚፈጽምበት ጊዜ ፡ ከዚሁ ያንድ ባታዮ ጦር በመቀሌ ምሽግ ውስጥ ሆኖ የብዙ ኢትዮጵያውያን ደም አፍስሶ ሳለ በወሃ ጥም ቢያልቅም ፡ ሊዋጋ የመጣ ጠላት ነውና ዐውቆ እጁን ካልሰጠ ዝም ብለው ቢሩጁት ያም ቢቀር ያለውል እጁን እንዲሰጥ አድርገው መሣሪያውን በሙሉ ቀምተው ወታደሩን በምርኮኝነት ይዘው ለሚፈልጉት የእርቅ ድርድር ሊጠቀሙበት በቻሉ ነበር ። ይኸንንም ሲያደርጉ ከጦርነትና ከወታደርነት ሕግ ወጡ ተብሉ በዓለም አያስፈርድባቸውም ነበር ።

ይኸን የመሰለውን ከዚህም የባሰውን ሁለት የአውሮፓ መንግሥታት በሚዋጉበት ጊዜ እርስ በርሳቸው ይፈጽሙታል ። ሲፈጽሙም ደንበኛ አፈጻጸም መሆኑ በማንም ዘንድ ይገመታል ። በዚህ ዘመን በቅኝ አገርነት ለመገዛት የተፈረደባቸው የአፍሪካና የእስያ አገር መሪዎች ግን ፡ ከፈረንጆች ጋር በሚዋጉበት ጊዜ የሚያደርጉት ነገር ሁሉ ሰበብና ቋፍ ያለበት ነው ። የአንድ አውሮፓዊ መቁሰልና መሞት አገር ወረራን የሚያስከትልበት ጊዜ ነው ። ይኸንንም የገዥነትና የተገዥነት መደብ ለይቶ የፈጠረው አውሮፓውያን በቴክኒክና በሌላው የመሠልጠናቸው ጉዳይ ነው ።

ዐፄ ምኒልክ ፡ በዕርቅና በሰላም ጣልያንን ለማስወጣት የመቀሌንም ጦር በነጻ ለቀው የርኅራኄ ፡ የሥርዓት መንገድ በተግባር የፈለጉበት ምክንያት ከአውሮፓ የሚሰነዘረውን ሰበብና ምክንያት ለማስወገድ ሲሉ ነው ። በዚህ ጊዜ የፈረንሳይና የመስኮብ መንግሥታት ለኢትዮጵያ

ነገር ግን ፣ እነዚህን ሰዎች ከነመድፋቸው ፣ ከነጥማቸው መስደዴ የሞኝነት አይምሰልህ ። ስለፍቅር(ስለሰላም) ያደረግሁት ነው ። ደግሞ እነዚህን ጥቂት ሰዎች አለነካቸውም ግስቱ መንግሥቱን ለማክበር ነው ። አሁንም ብትታረቁም ደኅና ፣ ጦርነትም ከከጀላችሁ እነዚህን ጨምራችሁ ጠቅላችሁ ኑ ።[1]

ፊልተር "እነዚህ ካልተቀቁ የሰላም ንግግር አይጀመርም" ብሎ ቃል ያለው ሐሰትን የተንተራሰ አባባል ነው ። ዐፄ ምኒልክ ዘንድ ያለውን ሰላም ፈላጊነት በመጠቀም ሰዎቹን ለማስለቀቅና ከዚያ በኋላ ለመዋጋት በኢጣልያኖቹ በኩል ያለውን የጋለ ፍላጎት ያውቀዋል ። የር ሱም አመጣጥ ጊዜ ለማግኘት መሆኑን ባለፈው ተመልክተነዋል ። ዳግማዊ ምኒልክም ባነጋገራቸው ፣ "እነዚህን መስደዴ የሞኝነት አይምሰልህ" ሲሉ የኢጣልያኖቹን ተንኮል እንደተገነዘቡት ያመለክታል። ነገር ግን ከላይ እንዳመለከትነው ፣ እነዚህን በመልቀቅ ለጠብ ምክንያትና ሰበብ የሚሆነውን ሁሉ በማስወገድ የዓለምን ፍርድ ለማግኘት በጣልያን ላይ ለማስፈረድ ሲሉ የተቻለውን ያህል እንደተጣጣሩ ይታያል ። ባንደ ወገን ደግሞ ፣ "ብትታረቁም ደኅና ፣ ጦርነትም ከከጀላችሁ እነዚህን ጨምራችሁ ኑ" ማለታቸው ለድል አድራጊነታቸው የተማመኑ ይመስላል ።

የዚህን የፖለቲካ ውዝግብ ደህና አድርጎ የሚያጤነው ወታደር የጋልያና ጦር ከነጦር መሣሪያው ጓዙን ጠቅሎ ከምሽጉ በወጣ ጊዜ ዘመድና ወገኑ የሞተበት ሁሉ በቁጭት እያወካ ለመታወም የጎ ቅናቱ ምልክት ባሳየ ቁጥር ፣ "ተው እርጋ" እያሉ ጠመንጃቸውን እንግበው ፣ በቀኝ እጃቸው ዘንግ ይዘው ኢጣልያኖቹን ከነባንዲያቻቸው ከበው ይከላከሉ የነበሩት በመቀሌው ጦርነት ይበልጥ የተጎዱት የሐረር የጦር ሹማምንት ናቸው ። በምኒልክ ቤተ መንግሥት ሥነ ሥርዓትን የተካኑት ወደ አውሮፓ በመሔድ ዘመናዊው የፖለቲካ ሙራ ገረፍ ያደረጋቸው ራስ መኮንን በፋንታቸው ይህን ግብረ ገብነት ለጭፍሮቻቸው አስተምረዋል ማለት ነው ። መኮንን ለምኒልክ አገረ ገዥና የጦር መሪ ከመሆናቸው አልፈው ፣ ልክ እንደ ውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የሚቆጠሩ የዲፕሎማቲክ ኃላፊ ጭምር ናቸው ። ሰላቶ ካፑቺ ለኢጣልያን ባለሥልጣኖች በጻፈው ሪፖርት ውስጥ ፣ "ከሁሉ የበለጠ የኛ ኃይለኛ ጠላት ራስ መኮንን ነው ፣ ምክንያቱም መኮንን ባንድ ወገን ብልህና ታታሪ ፣ በሌላ ወገን የምኒልክ ታማኝ በመሆኑ ነው" የሚሉ ቃላት አስፍሯል ።[2]

---

1 ታሪክ ዘመን ዘዳግማዊ ምኒልክ ምዕ.43 ገጽ 249,250
2 I Russi in Etiopia - Carlo Zaghi, P. 76.



ከመቀሌ ምሽግ የጋልያና ጦር ከመውጣቱ በፊት ስምምነት እንደ ተደረገ የኢጣልያ ባንዲራ ወርዶ ነጭ ባንዲራ ተሰቅሎ ነበር። አሁን ደግሞ ፣ ምሽጉን በሙሉ እጅ ካደረጉ በኋላ በጅሮንድ ባልቻ ከንጉሠ ነገሥቱ ታዘው ሐደው ግባት (የደስታ ተኩስ) እየተተኮሰ የኢትዮጵያ ባንዲራ በገሃድ ተሰቀለ ።

ማናቸውም ዝግጅት በዚህ ዓይነት ከተፈጸመ በኋላ ፣ ጋልያና ከንጉሠ ነገሥቱ በተሰጠው በቅሎ ተቀምጦ ጉዞው ተጀመረ ። ምንም እንኳን ለጠቅላላው የበላይ ጠባቂነት የራስ መኮንን ቢሆንም ፣ እርሳቸው ደግሞ ፊታውራሪ ደሳለኝን በቅርብ ሆነው እየጠበቁ አዲግራት እንዲያደርሱት አዘዋቸው ነበርና በማናቸውም ዝርዝር ጉዳያቸውን ጣልያኖቹ በአቶ ወልደ እግንኤል አስተርጓሚነት ይጠይቁ የነበረው ፊታውራሪ ደሳለኝን ነበር ። ለፊታውራሪ ደሳለኝም ረዳት ከዚህ በፊት በዕርቅ ምክንያት ወደ መቀሌ ምሽግ ተመላልሰው የነበሩትና ከጋልያናም የተዋወቁት ብላታ እንግዳ የሚባሉ ነበሩ ።

እ.ኤ.አ. ጥር 22 ቀን ወደ ማታ ጋልያና ከነግዙ ሰፈሩን ለቆ በራስ መኮንን ጦር እንደ ተከበበ ፣ የኢትዮጵያን መኳንንት የበረከቱ ድንኳኖች እያቋረጠ ወጥቶ በቅርብ ከሰፈረ በኋላ ፣ በማግሥቱ እዚያው ውሎ ሆና በጥር 24 ቀን እሱና ጦሩ ጉዟቸውን ቀጥለው የንጉሠ ነገሥቱ ቀዩ ድንኳን የተተከለበትን የማባቦን ሜዳ እያዩ ወደ ማይ መኽያን አመሩ ። በዚህ ዓይነት በየመንገዱ እያረፉ በጥር 28 ቀን እደባ ደርሰው ሳለ ፣ በመካከሉ አስቀድሞ እንደተነጋገሩት ስለእርቅ ጉዳይ ከባራቲዬሪ ትልቅ ሰው ተመርጦ ይመጣል ተብሎ ይጠበቅ ነበርና ሳይመጣ ስለዘገየ ራስ መኮንንም እደባ ላይ ሰፈሩ ። ጋልያና እስከ ድንኳናቸው ድረስ እየሔደ ፣ "ጉዟችን ዘገየብን" እያለ ሲከራከር እርሳቸውም ፣ "ባራቲዬሪ ማጆር ሳልሳን እልካለሁ ብሎ እስካሁን ባለመላኩ ቃሉን አልጠበቀም" እያሉ ሲመልሱ ቆዩና በመጨረሻ ሹማምንቱ መያዣ ሆነው እንዲቆዩ ተደረገ ። ጋልያናና ጓዙ በፊታውራሪ ደሳለኝ መሪነት ወደ አዲግራት ጉዟቸውን ቀጥለው በሐውዜን አልፈው እዲጋ ሐሙስ ደርሰው የሁለት ቀን ዕረፍት አደረጉ ። አዲግራት በናፍቆት የሚጠበቀው ጋልያናና ጓዙ እዲጋ ሐሙስ የመድረሳቸው ወሬ ሲሰማ ፣ ጠቅላይ አዝማቹ ሌተና ጀኔራል ባራቲዬሪ ራሱ እንደ ታጀበ ጋልያናን ለመቀበል ጉዞ ጀምሮ በጥር 30 ቀን ተገናኙ።

በመንገድ በተገናኙ ጊዜ ፣ ጀኔራሉ ከፈረሱ ላይ ወርዶ አንገቱን አንቆ ሲስመው ሌሎቹ የጦር አለቆች የቀሩትን እያቀፉ ይስሙ ነበር ። "የኢትዮጵያ ጦር በወሃ ጥም ይጨርሳቸዋል እንጂ በዋዛ አይለቃቸውም ። ከምሽጉም እንዲወጡ ያደረገው በእጁ ከገቡ በኋላ እንደ

ከዚህ ቀጥሎ ያለውን ደብዳቤ ለኢጣልያ ንጉሥ ጽፈው ለባራቲዬሪ ላኩለት ።

ሞዓ አንበሳ ዘእምነገደ... ለግርማዊ ኡምቤርቶ የኢጣልያ ንጉሥ ሰላም ለርስዎ ይሁን ። ሰላምና ወዳጅነት መፈለግዎን ጄኔራል ባራቲዬሪ ስለነገረኝ ደስ ብሎኛል ። የራሴን የክርስቲያንነት እምነት ለመግለጽ ስል በእንዳ ኢየሱስ ምሽግ ተከበው ተጨንቀው በወኃ ጥም አልቀው በእግራችን ውስጥ ሲረገጡ የቀረቡትን ከነዕቃቸው በመልካም ሁኔታ በራስ መኰንን ሸኝነት አስወጥተን ሰደድናቸው ። አሁንም ተነጋግሮ ስለ ሰላም ሊቆርጥ የሚፈልጉትን ሰው ያስታውቁኝና እኔም ጠቡ ቀርቶ ስለ ሰላም የሚነጋገረውን ወኪሌን እደርጋለሁ ።

ይኸን ከጻፉና ለንጉሡ ይልክ ዘንድ ለባራቲዬሪ ከላኩ በኋላ ዳግማዊ ምኒልክ ከሰፈሩበት ከመቀሌ በማግሥቱ ተንሥተው ወደ ሐውዜን ፥ ከሐውዜን ወደ ፈረስ ማይ ፥ ከፈረስ ማይ ወደ ሳውሪያ ፥ ከዚያም ወደ ግራቸው ታጥፈው በገንደብታ አድርገው ዓድዋ ገብተው በተለይ ፋሐ ከሚባለው ጥንታዊና ታሪካዊ ቦታ ሠፈራቸውን አደረጉ ። ሐውዜን የነበሩ ጊዜ ወደ እዲግራት ስለቀረቡ ፥ ይወጉናል የሚል ፍራቻ ኢጣልያኖቹ አድርባቸው ለጦርነት መሰናዳት ይዘው ነበር ።

ዋናው አዝማች ፥ ያኔ ምኒልክን ደብዳቤ ራሱን ወደ ሮማ ለመላክ ጊዜው አጣዳፊ ስለሆነ ፥ የደብዳቤውን አሳብ በቴሌግራም አስታውቆ በጠቅላላው የመንግሥቱ አሳብ ምን እንደሆነ እንዲገለጽለት በጥር 28 ቀን ጠይቆ ስለነበረ ፥ ከውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ከባሮን ብላን ዘንድ እንደዚህ የሚል ቃል ለለቱን መጣለት ።

ባሁኑ ለጦርነት በተሰለፍንበት ሰዓት ለወደፊቱ በኢትዮጵያ ላይ የሚኖረንን አቅዋማችንን የሚያረጋግጥ አንድ የጦርነት ድል ኢጣልያ ሳታገኝ አሁን በሚደረገው የሰላም ውል ምንም ዐይነት ጥቅም እንደ ማይገኝ የንጉሡ መንግሥት ያምናል ።[1]

ጠቅላይ ሚኒስትሩ ክሪስፒ ደግሞ በበኩሉ ፥ "እምባ አላጌና መቀሌ ክብር ቢኖረውም ፥ ሁለት ውድቀት ያገኘንባቸው ናቸው ። የኢጣልያ የንጉሡ ክብር በእጅህ ነው ያለው" ሲል አስተላለፈለት ። ትርጓሜው በአላጌና በመቀሌ መካከል ምንም እንኳን የኛዎቹ ክብር ያለው የመከላከል ሥራ ቢሠሩም ፥ መጨረሻው መሸነፍ ስለሆነ እንደ ምንም ተዋግተህ አሸንፈህ አንድ ድል አግኝተህ ክብራችንን አድስ የሚል ነው ። በነዚህ ዐይነት ከዚህ ከሁለት የኢትዮጵያ ድሎች በኋላ አንድ የመመለሻ ድል በጣም እንደ ናፈቃቸው ይታያል ።

1 Italia ed Etiopia... Conti - Rossini... PP. 257 - 264; Gli Italiani in Africa Orientale, A. Del Boca, PP.629 -630; The Campaign of Adwa and the Rise of Menelik, Chap. VII, PP. 237 -238.



ስለዚህ ባራቲዬሪ የንጉሠ ነገሥቱ ጦር ወደ ዓድዋ ሲጓዝ ፥ ሐውዜን በሰፈረበት ጊዜ ከእዲግራት ወጥቶ መዋጋት እየፈራው ፥ ማሸነፍም እየጓጓ ደግሞ እየፈራና እያመነታ ፥ በዚሁ መካከል ጠቅላይ ሚኒስትሩም የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩም ጦርነቱን እየገፉት ለሚያስተላልፉለት ቴሌግራም እርሱም በበኩሉ የኢትዮጵያን የጦር ድርጅት እየ ጠቀሰ በሌላው ወገን ደግሞ ፥ በገዳሪፍ ደርቡሾች ስውጊያ መሰብሰባቸውን በመግለጽ ለጊዜው ውጊያው አስቸጋሪ መሆኑን ገልጾ ነበር ። በዚህም ዓይነት ብዙ ውዝግብ ካለቆቹ ጋር ከገጠመ በኋላ መደምደሚያውን ከኢትዮጵያ ጋር የእርቅ አሳብ በውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ተነድፎ ቀደም ብሎ ተልኮለት ነበር ። ከሮማ የተላከው ኩራትና ዕብሪት የተሞላበት የዕርቅ ድርድር የሚከተለው ነው ።

፩ኛ. የኢጣልያ መንግሥት እስከ አሸንጌና እስከ ተከዜ ድረስ ሙሉ ትግራይን ጠቅሎ በቀጥታ ገዥነት እንዲኖረው ፥

፪ኛ. የኢጣልያ ንጉሥ ኡምቤርቶ በቀረው እስከ ሱማልያ ፥ ከወዲህም እስከ አዋሽ ወንዝ መጨረሻ ድረስ ባለው በኢትዮጵያ ግዛት ላይ የበላይነቱ እንዲታወቅ ፥

፫ኛ. ለውጭው ዓለም የኢትዮጵያ ወኪልና ጠባቂ ኢጣልያ መሆኑ በግልጽ እንዲታወቅና በኢትዮጵያ ያሉ የውጭ አገር ሰዎች (ይኸውም ማለት ለኢትዮጵያ የሚረዱት የመስኮብና የፈረንሳይ ተወላጆች) እንዲወጡ ፥

፬ኛ. ንጉሠ ነገሥቱና የአውራጃ ገዥዎች ቁጥሩን ከሚወስንላቸው አልፈው የኢጣልያ መንግሥት ሳይፈቅድ ወታደር እንዳያደራጁ ፥

፭ኛ. ራሶችና ያውራጃ ገዥዎች ከመሾማቸው በፊት ለፈቃድ የኢጣልያ መንግሥት እንዲጠየቅ ፥

፮ኛ. በኤርትራ አንድ ወራሪ ቢመጣ ንጉሡና ራሶቹ ኃይላቸውን ይዘው ወጥተው እንዲረዱ ፥

፯ኛ. በንጉሡና በራሶቹ መካከል ፥ በራሶቹና በሹሞቻቸው መካከል ክርክር ቢፈጠር ጉዳዩ ለኢጣልያ መንግሥት ቀርቦ እንዲወሰን የሚል በ7 አንቀጽ ላይ የተመደበ ነበር ።[1]

ጄኔራል ባራቲዬሪ ይኸን የመሰለ የማይታሰብ የስምምነት አሳብ ቢደርሰውም ፥ ራሱ እንደ ገለጸው በንጹሕነቱ የሚኮራና ተዋጊ ሕዝብ የተዘጋጀ ጦር እያለው ተዋግቶ ከመሸነፉ በፊት ይኸን የመሰለውን

1 Tomasso Salsa, Il Canevari E Comisso PP 288—290

የዕርቁ ነገር እንደቀረ ይቁጠሩት ። ከኛ እያንዳንዱ የፈለገውን ነገር ለማድረግ ይሆንለታል” ማለቱ ፤ ከጠረፍ እስከ አዲስ ድረስ ሙሉው የትግሬ ግዛት ካልተሰጠን ጦርነት ለማድረግ መዘጋጀታችንን ይወቁት ማለቱ ነው ። ስለዚህ ደብዳቤ ዐፄ ምኒልክ መልስ መስጠታቸው በጸሐፊ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴም ፤ በጄኔራል ባራቲዬሪም በሌላም መጽሐፍ አልተገኘም ። የሆነ ሆኖ ፤ ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ሁለቱም ወገኖች አሳብ ለአሳብ በግልጽ ስለ ተዋወቁ ከቀድሞ የበለጠ ለጦርነቱ ይዘጋጁ ዠመር ።[1]

1 Gli Italiani in Africa Orientale, A. Del Boca, PP. 635-636.





ዐፄ ምኒልክ በዓድዋ ጦርነት ጊዜ
ከኔላ ቴራ ዴ ንጉሥ ከተባለው መጽሐፍ

# ምዕራፍ ሠላሳ አራት

የጎራስ ሰብሉት ወደ ኢትዮጵያ ጉራ መመለስ — የአንቶኒሊ ግስወንቶቲያ
የኢትዮጵያ ጦር በግራ ፣ የኢጣሊያ ጦር በምሥራ
ለመገኘ ልል መፈለለጋቸው ።

ንጉሠ ነገሥቱ በፋኖ ከአቴኒ ማይፉ ፣ ከንጉሥ ተክለ ሃይማኖትና ከሰራተኛም ጋር በሰፈሩበት ሰዓት ሁለት አስደሳች ነገር ተምሯቸዋል ። አንደኛው ፣ ከራስ መንገሻ ዮሐንስ ጋር ባላቸው ጠብ የተነሣ ለኢጣሊያኖች ገብተው ያስገዙ የነበሩት የራስ ስብሐትና የደጃች ሐጎስ ተፈሪ ወደ ኢትዮጵያ መንግሥት ጉራ መመለስ ነው ። ሁለቱም የስሙ ጥሩው የአጋሜ ባላባት የደጃች ሰባጋዲስ ተወላጆች ስለሆኑ ፣ የአጋሜና ይንስ ይብዛ የእንደርታም ሕዝብ ስለሚከተላቸው ፣ እነዚህ ሁለት መኳንንት ቀድሞ ከኢጣልያ ጋር በነበሩበት ጊዜ በማናቸውም ረገድ በወታደር ምልመላ በስንቅ አቅራረብ በወሬ ስለላ ጣልያንን ይጠቅሙበት ከነበረው ጉራ አሁን ወደ ወገናቸው ሲመጡ ፣ ለኢትዮጵያ የሚሰጡትና በውነትም የሰጡት ጥቅም ብዙ ሲሆን በዚያው መጠን የኢጣልያን የጦር ጉራ ከተኛ ጉድተውታል ። የኢጣልያ ጠቅላይ ሚኒስትር ክሪስፒና ጠቅላይ የጦሩ አዛዥ ባራቲዬሪ ፣ "ኢትዮጵያ አንድነት የሌላት አገር ነች ። ጦርነቱ ገና ሳይጀመር የኢትዮጵያ መሳፍንትና መኳንንት ምኒልክን ከድተው ወደያውራጃቸው ይመለሳሉ ። ወይም ወደኛ ይገባሉ" ብለው ሲጠባበቁ ፣ ይልቁንስ ከነርሱ ጋር የነበሩት ወደአገራቸው ጉራ መግባት ጀመሩ ።

ሁለተኛው ያጼ ምኒልክና የመኳንንቱ ደስታ በአውሳ የመሐመድ አንፋሪ የመጀንቱን ወሬ መስማታቸው ነው ። ጦርነቱም በጥር 12 ቀን ተፈጽሞ ይኸን ወሬ ለማብሰር ከአውሳ የመጣው መልእክተኛ ቶሎ ወደ ምኒልክ ዘንድ የደረሰው ፣ በየካቲት 22 ቀን የዓድዋ ጦርነት ዋዜማ ላይ ነው ። የዚህም ሁሉ ውጤት የኢትዮጵያን ወታደር ሞራሉን ከፍ እያደረገው ሲሔድ የኢጣልያኖችን ዝቅ እያደረገው መጣ ።

እስካሁን ድረስ ንጉሠ ነገሥቱን በጣም ያስቸገራቸው ፣ አንደኛ ኢጣልያኖች እንደዚያው እንደ መቀሌ በእዲግራት ፣ በእንቲጮና በሳውሪያ መሽገው ከምሽጋቸው ውስጥ ሆነው መጠባበቅ እንጂ ወደ

ሚያ ወጥተው እስመጣጠማቸው ፤ ሁለተኛ ጦርነቱን ከፈሩት ደግሞ ታርቀው አገር ለቀው እስመሔዳቸው ፤ ሦስተኛ ቤቱን ንብረቱን ትቶ ለጦርነት የመጣው ቁጥሩ ከ80,000 እስከ 100,000 የሚደርሰው ጦርና የርሱ ተከታይ አሽከር ገረድ ቤቱን ለቆ ከወጣ አምስት ወር ስለሆነው ፣ በዚህም ጊዜ የያዘው ስንቅ በሶውም ፣ ጭብጦውም ፣ ቆሎውም አልቆበት ስለሚራብና በዙሪያው የሚገኘውን አገር ፣ ትእዛዝ እየተላለፈ ፣ በመዝረፍ ከባላገሩ ጋር ጠብ ማብቀሉ ፣ ያለበት አገር በከብትና በእህል ረገድ ይኸን ያህል ስለማያወላዳ ፣ ተዋጊውን ወታደር እየቀለበ ለከብቱም ሁሉ ሣር እያቀረበ ሊያዋጋ አይችልም ። ከደቡብ አውራጃዎች እያጓዙ ወታደሩን የማዋጊበ ነገር በዚያን ጊዜ የማገናኛው ድርጅት ጉድለት በተለይ ሰሩት አገር የተጓላ ባለመሆን ችግር ፈጥሯል ። እስከዚህም እስከ አምስት ወራት የተደረሰው በዚሁ በአህያና በአጋሰስ እየተጫኑ ፣ በሰውም ትከሻ ከሩቅ አውራጃዎች በሸማምንቱ ፣ በጭፍራው ፣ በገባሩና በገበሬው ትጋትና ድካም የመጣ ነው ።

ዋና ስንቅ መስፈሪያው ወረይሉና ቦሩ ሜዳ ላይ ነው ። ከሸዋ የሚመጣው ወታደር ሁሉ በያዘው ስንቅ ተጨማሪ ቦሩ ሜዳ ላይ ተሰፍሮ እየተሰጠው ነው ጉዞውን ወደ ሰሜን ቀጥሉ እዚህ ሰዓት የደረሰው ። ቦሩ ሜዳና ወረይሉ (ሆረው) የስንቅ ኃላፊ የሆኑት ቢትወደድ አጥናፌ ተከለ ዮሐንስ ፣ ከሸዋና ከየትኛውም ክፍል በከብትም በሰው ትከሻም የሚመጣውን ዱቄቱንም ፣ ጥራጥሬውንም እየተቀበሉ ወደጦሩ ማገባር በመላክ ታላቅ አገልግሎት ማድረጋቸው ቢታወቅም ፣ ጊዜው በተራዘመ መጠን ችግሩ በጣም እየከበደ ይሔዳል ።

ዳግማዊ ምኒልክም ፣ መሳፍንቱም ፣ መኳንንቱም ፣ ወታደሩም በዚህ ሁሉ ችግር መካከል ስለሚገኙ ፣ ይኸን ሁሉ ጦር ይዘው ንጉሠ ነገሥቱ ወይ ካልተዋጉ ወይ ካልታረቁ ፣ እንደዚሁ ዝም ብለው ባሉበት ሥፍራ ለረጅም ዘመን መቆየት አይሆንላቸውም ። በዚህ ምክንያት ከፅሃ ተነሥተው መረብን አልፈው ሐማሴንንና አከለ ጉዛይን ለመውጋትና ከዚሁ ከኤርትራ በተለይ ከምጽዋና ከአሥመራ ወደ አዲግራት ፣ ወደ ሳውሪያ ለዋናው የኢጣልያ ጦር ሠራዊት የሚመጣውን የመጓሪያና የምግብ እርዳታ ለማቋረጥና ጣልያኖቹን አስገድዶ እንዲዋጉ ለማድረግ ታስቦ በቅድሚያ እነሊቀ መኳስ አባተ ወደ መረብ ቦታውን ለማጥናት ተላኩ ፤ እነርሱ ደግሞ ፣ "የመረብ ወሃ ስለ ደረቀ እንኳን ለጃንሆይና ለሠራዊቱ ለእኛም እዚህ ላለነው አልበቃንምና ጃንሆይ እዚያው ቢቆዩ ይሻላል" የሚል መልእክት አስተላለፉ ። የነርሱንም ሐሳብ በኋላ እነራስ መንገሻ ዮሐንስ አጽድቀውታል ።



ስለዚህ እልፍ የመሔዱ ጉዳይ በወሃ እጦት የተነሣ ሳይሳካ ቀረ ። አሁን በፊታቸው ያለው ወይ ከምሽጉ ድረስ ሔደው የኢጣልያን ጦር መውጋት ወይም በልዩ ልዩ ዘዴና ወታደራዊ ንቅናቄ (ማንቨር) የጠላት ጦር ከምሽጉ እንዲወጣ ማስገደድ ነው ። ወደ ምሽጉ ሔዶ መዋጋት ሕዝብ ማስጨረስ መሆኑን ከመቀሌውም ጦርነት ተምረውታል ። አሁንም በቅርብ ያሉት እነራስ መንገሻም ፣ ሌሎችም ወደ ምሽግ ተጠግቶ የመዋጋቱ ነገር እንዳይታሰብ በጥብቅ አስጠንቅቀዋል ።

ስለዚህ ፣ በኢጣልያኖች በኩልም ፣ "የኢትዮጵያ ጦር ወደ ምሽጉ መጥቶ ካልወጋን በቀር ሜዳ ላይ ወጥተን አንችለውምና በተቻለ መጠን ከምሽግ ወጣ እያሉና እየተንኳኩሉ ወደ ምሽግ በመመለስ በገዶት ወደ ምሽግ መጥቶ እንዲዋጋ ማድረግ ነው" እያለ ለጣልያኖቹ የሚመክረው ብዙ ነው ። በነርሱም በኩል ተመሳሳይ ችግር ስላለባቸው እንዲያውም ፣ "ከምሽግ ወጥቶ ወደኋላ ወደ አሥመራ መመለስ ይሻላል" ብለው አሳብ የሚያቀርቡም ነበሩ ይባላል ።

ከዚህ ቀደም እንዳመለከትነው ፣ በአርጀንቲና የኢጣልያ ወኪል ሆኖ የተቀመጠው ኢትዮጵያን ዐውቃለሁ ባዩ አንቶኔሊም ካለበት ከሩቅ አገር የሚልከው ምክር ይኸንን የሚያሳስብ ነው ። የዓድዋ ጦርነት ሊደረግ ስምንት ቀን ሲቀረው እነራስ ስብሐት የኢጣልያን ጉራ ትተው ከመጡ ወዲህ ፣ ይኸው ሰውዬ እ. ኤ. አ. የካቲት 21 ቀን 1896 ዓ. ም ለጠቅላይ ሚኒስትሩ በላከው ማሳሰቢያ ውስጥ ፣

> “. . . ከዚህ በፊት ራስ ስብሐትን መጠርጠር ያስፈልጋል ብዬ በቴሌግራፍ አስተላለፈ የነበረው እነሆ አሁን ከሁለት ወር በኋላ መሸፈቱን (ወዳዬ ምኒልክ መሄዱን) ሰማሁ. . . አሁን በደረስንበት ሁኔታ በዚህ ዓመት በተቻለ መጠን ዓላማችን መከላከል እንጂ ማጥቃት የለብንም ። መቶ ሚሊዮን(ሊሬ) እንኳን ቢኖረን በዚህ ዓመት የኢትዮጵያን የቁጣር ግዛት ማለመን አንችልም ። ከሁለት ወር በኋላ የዝናም ጊዜ ይጀምራል ። ከራት ወር በኋላ ደግሞ በሚያጥለቀልቀው ዝናም ወንዞቹ ሁሉ በጎርፍ ይሞሉና መንገድ ሁሉ ይዘጋል ። ከሌላ ስሕተት ላይ እንዳንገና ካልወደቅን በቀር እንደ ምንም እየተከላከሉ ቆይቶ ምኒልክን ከነሠራዊቱ ወደ መጣበት ሲመለስ ማየቱ የተሻለ ነው ። በክረምቱ ወራት እስከ ተቅምት ድረስ ባለው ጊዜ ውስጥ ለሚመጣው ዘመቻ በሚገባ መደራጀት ነው ። ባናበዛው ኖሮ ምኒልክ እስከዚህ ሊወጋንም ባልፈለገ ነበር . . .”[1] የሚል ይገኝበታል ።

1 La Prima Guerra d' Africa, F. Crispi, PP. 295 - 297

ውስጥ በወቅ እንደ መሆን መጠን የአንቶኔሊ ምክሩ ተቃሎ የሚታይ አይደለም ። በእውነትም የኢጣልያ ጦር ከምሽግ ወጥቶ ባያጠቃ የዐፄ ምኒልክ ጦር ወደ ምሽጉ ሔዶ ማጥቃትም ፣ በትግሬም ያን ሁሉ ጦር ይዘው ለብዙ ጊዜ መቆየትም ስለማይሆንላቸው ነገሩ ግራ አጋቢ ነበር ። ለውጊያው ተስፋ ቆርጠው ወደ ሸዋ ቢመለሱም ፣ ባንድ ወገን ከየካቲት ወይም ከመጋቢት እስከ ጥቅምት ባለው ጊዜ ውስጥ አዳዲስ ወታደር እየመለመሉ ከኢጣልያ አገርም ጦር ጨማምሮ ለመደርጀት ያመቸዋል ።

ራሱ ጠቅላይ አዛዡ ፣ ጄኔራል ባራቲዬሪ በበኩሉ ከምሽግ ወጥቶ በሜዳ መዋጋትን ስለፈራ ፣ አበሾቹ እስከ ምሽጉ ድረስ ሔደው ቢወጉት ድልን እንደሚያገኝ ያምን ነበር ። በዚህ ምክንያት ፣ ዐፄ ምኒልክ ካሉበት ከዓድዋ የርሱ ጦር ወደ መሸገበት ወደ እንትጮ ጠጋ ብለው በገንደብታ በሰፈሩበት ጊዜ ውጊያና ድል ለናፈቀው አለቃው ለክሪስፒ እ. ኤ. አ. በየካቲት 9 ቀን 1896 ዓ. ም. ባስተላለፈው ቴሌግራም እንደዚህ ብሏል ።

> የኛና የሸዋ ጦር በትንሽ ኪሎ ሜትሮች ርቀት ሁለቱም ጥሩ ጥሩ ስፍራ ይዘው ፊት ለፊት ሆነው ይጠባበቃሉ ። እምሽጋችን ድረስ መጥተው ሊዋጉን መቁረጣቸውን ሰላዮቹ ገልጸውልኛል ። በርግጥም ከምሽጋችን መጥተው ቢወጉን ድል ማድረጋችን እርግጥ ነው ። ከኛ የበረከተው ጦርና ደህና ሥፍራ ይዞ የሚጠብቀንን ሄደን ብንወጋው ድሉ አጠራጣሪ ነው ።... ድሉ ቀንቶን ጠላት ቢሸሽም ወጣ ገባ በሆነ አገር የኛ የነጭ ወታደር እንደ ጥቁሩ ጠላትን እንደልብ ሊያባርር አይችልም ።[1]

በዚህ ጊዜ ፣ የኢትዮጵያና የኢጣልያ ጦር አንዱ ቅኝ አገር ለማግኘት ፣ ሌላው ያገሩን ነጻነት ለመጠበቅ ለጦርነት በተሰለፉበት ሰዓት ሁለቱም ድልን ሲመኙ ፣ ወደዚህ ድል የሚያመራውን ቁርጠኛ ጦርነት ለማድረግ የሁለቱም ፍላጐት ለየብቻ መሆን ግልጽ ነው ። ከዚህ በላይ ላለቃው ለክሪስፒ እንዳስተላለፈለት ፣ "ዐፄ ምኒልክ ካሉበት ከገንደብታ እስከ መሸግሁበት እስከ እንትጮ ፣ እስከ ሳውሪያ ድረስ መጥተው ቢወጉኝ ምሽጌን ይዤ በመዋጋት ድልን አገኛለሁ" ብሎ በናፍቆት እንደሚጠባበቅ ሁሉ ዐፄ ምኒልክም ፣ "የተደበቀበትን ምሽግ ለቆ ወደ ውጭ ወደ ሜዳ ወጥቶ ምንው በተዋጋሁና

1 Memoire d' Afrique . . .PP. 349-350



በለየልን" በሚል ምኞት ተደብቀው ይጠባበቃሉ ። እንዲህ "ወደ ምሽጉ ሔደው አይዋጉ ፤ ሠራዊትዎን ያስጨርሳሉ ። ያንንም ከሜዳ ሔደህ አትግጠም ሠራዊትህ ያልቃል" የሚላቸው የየግል መካር በብዛት አሏቸው ማለት ነው ። ቢሆንም ፣ ሁለቱም ከጥንቃቄና ራስን ከመጠበቅ ጋር ወታደራዊና ስልቱዊ ንቅናቄ ማድረጋቸው አልቀረም ። ዐፄ ምኒልክ ከነበሩበት ከዓድዋ ተንሥተው ወደ ገንደብታ ፣ ከዚያም ወደ አላይ መጥተው ሰፈሩ ። ጣልያኖችም ከተከዙ በስተደቡብ ያለውን ሳውሪያ (ሱዋሪያ) የሚባለውን ይዘው መሸጉ ። ከዚህም ቀጥሎ ባለው ጊዜ ውስጥ አንዳንድ ጊዜ የኢጣልያ ሹማምንት ፣ ሦስት መቶም አምስት መቶም ወታደር እያስከተሉ አገርና ስፍራ ምርመራ ሲወጡ እነቀኛዝማች ታፈሰ በሩቅ እያዩ ፣ ሲያባርሯቸውና እስከ ምሽጋቸው እያደረሱ በመመለስ ጦርነት ሲያደርጉ ሰንብተዋል ። ራስ ስብሐትና ደጃች ሐጎስም ባንድ ወገን የጠላት ወታደር የሚመላለስበትን መንገድ በሚያውቁት አገር በአጋሜና በእንደርታ እየሔዱ ሲያስናክሉና በግድ መሬት እንዲታወሩ እያባቁ በምቁበት ቀን ኃይለኛ ጦርነት ማድረጋቸው አልቀረም ።

ብዙ ጊዜ ደግሞ ፣ የኢትዮጵያ ወታደሮች የደፈጣ ጦርነት እያደረጉ ጣልያኖቹን ያበሳጩአቸው ነበር ። ዝም ብለው መንገድ አሳልፈው በጫካ ተደብቀው ተኳኩሰው ከተንኮሷቸው በኋላ ጣልያኖቹ ውጊያ ሲያምራቸው ይሰወሩባቸዋል ። ስለዚህ አንድ ካርደላ የሚባል ሻምበል በጻፈው መጽሐፍ ፣ "እነዚህ ጥቁሮች ፈሪዎች ናቸው ። ሲያዩን ይሸሻሉ ፤ ተበታትነን ስንጓዝ ደግሞ ይወጉናል ጭካኔያቸውም ከፍ ያለ ነው [1] . . ." ሲል አመልክቷል ። የነርሱ ከምሽግ አለመውጣት በፍርሃት መሆኑን ግን ፣ ይኸው ካርደላ ሊጠቅሰው ስለአልፈለገ ፤ አድላዊ ጸሐፊ ነው ማለት ይቻላል ። ካርደላ ፣ "እነዚህ ጥቁሮች ፈሪዎች ወይም የፈሪ ጨካኞች ናቸው" ብሎ የጻፈውን የመቀሌን ጦርነት የተካፈለው ኮሎኔል አሚን—ዶላጂ "ባበሾች ላይ ፈሪ የፈሪ ጨካኝ ብለህ የጻፍከው ከውነት የራቀ ነው ፣ በመቀሌ ጦርነት ፊት ለፊት እየተዋጉ በምሽጋችን ፊት የሬሳ ቁልል ትተው የለምን !" በማለት አስተባብሏል ። ወደፊት ይኸው ካርደላ በዓድዋ ሲዋጋ ስለ ተማረከ ፣ የሐበሾቹን ጀግንነት የራሱን ፈሪነት በልቡ ሳይገነዘበው አይቀርም ።

ይሁን እንጂ ፣ ቀናው የኢጣልያ ጦር በእንትጮና በሳውሪያ መሽጎ ስለ ተቀመጠና ወጥቶ ከመዋጋትም ስለዘገየ ፣ ዐፄ ምኒልክ ከዚህ ቀደም

1 Da Adua al Congo ,E. Cardella, PP. 17-18

እንዳሰቡት ፣ የመሸገውን ጦር እንዳለ ትተው በግራ በኩል ወደ ሐማሴን ለመዝለቅ ያሰቡትን ጎንደብታን ለቀው ወደ እሳይ (ያባ—ገሪማ ጉልት) ከዚያም ወደ ዓድዋ ዘልቀው ሰፈሩ ። በዚያ ሳሉ ምናልባት ኢጣልያኖች መጥተው በድንገት ውጊያ የገጠሙ እንደሆነ በማለት ለጥንቃቄ ራስ መንገሻ ዮሐንስ ፣ ራስ ሚካኤል ፣ ራስ ወሌ ፣ ራስ ቢትወደድ መንገሻ ፣ ራስ መኰንን ግንባር ቀደም ሆነው በአባ ገሪማ በኩል ተሰልፈው እንዲጠብቁ ተደረገ ። ዳሩ ግን ፣ ጣልያኖቹ ከሰፈራቸው ሳይነቃነቁ ዐፄ ምኒልክም ከአባ ገሪማ ዓድዋ መጥተው መሣሪያቸውን እንደያዙ ሁሉም ሲጠባበቁ ዋሉ ።

ዐፄ ምኒልክ ፣ ከዚህ በፊት ወደ ኤርትራ ለመዝመትና ጣልያኖችን ከጀርባ ለማጥቃት እንዲያጠኑ እነሊቀ መኳስ አባተን ልከው እንደነበረ አሁን ደግሞ ራስ መንገሻ ዮሐንስን ፣ ራስ መኰንንን ፣ ፊታውራሪ ገበየሁን ፣ ፊታውራሪ ተክሌንና ሊቀ መኳስ አድነውን "ወደፊት ሒዳችሁ አዲኳላ ሰፍራችሁ ጠብቁኝ ፣ እኔም ከናንተ ቀጥዬ እመጣለሁ" ብለው ልከዋቸው ነበር ። እነሱም ታዘው ከሔዱ በኋላ መረብ ሲደርሱ የመረብን ወንዝ ደርቆ ስላገኙት ፣ ከዚህ በፊት እነሊቀ መኳስ አባተ እንዳሉት ፣ "እዚህ የጃንሆይ መምጣት ይቅርና ለኛም እዚህ ላለነው የመረብ ውሃ ስለደረቀ ፣ ሰውም ከብትም ከትናንት ጀምሮ ውሃ ለማጠጣት ተቸግረናል" የሚል መልስ ወደ ንጉሠ ነገሥቱ ላኩ ። ስለዚህም ወደ ሐማሴን ዘልቆ ኢጣልያኖቹን በጀርባ የመከበብና ቅኝ አገር አድርገው የያዙትን ሐማሴንን ፣ እከለ ጉዛይንና ሰናፌን የመውረሩ ነገር ቀረ ።

መረብንም ተሻግሮ ለመዝመት የታሰበበት አንደኛው ጉዳይ ፣ "የያዝነው ግዛት የሚወረር ከሆነ ከምሽጉ ወጥቼ ብዋጋ ይሻላል" ብሎ የጣልያን ጦር ከምሽጉ እንዲወጣና እንዲዋጋ ለማድረግ የታሰበ ዘዴ ነበር ። የሆነ ሆኖ ፣ በመጨረሻ ለሰውም በተለይ ለከብት ሣርና ውሃ በማይጠፋበት በዓድዋ መቆየቱ ይሻላል ተብሎ ተመክሮና ዋናው ሰፈር በዓድዋ እንዲሆን ተወሰነ ። ቢሆንም ጣልያኖች ዐፄ ምኒልክ እስከ ሐማሴን ዘልቀው ከጀርባ ለመውጋት ያላቸውን ሐሳብ ከሰላዮቻቸው በሰሙ ጊዜ በጣም ሥግተው ነበር ። የኢትዮጵያ ጦር ወደ ሐማሴን ሔዶ በምጽዋ በኩል ከአሥመራና ከአዲኡግሪ ሳውሪያ ላለው ለዋናው ጦራችን ስንቅም ፣ መሣሪያም የሚያመላልሰው የተቋረጠ እንደሆነ ጦሩ ዙሪያውን ተከቦ በመቀሌ እንደ ሆነው ዓይነት ችግር እንዳይፈጠር በመሥጋት የኢጣልያ ጦር አዛዥ አንድ ብልሃት መፍጠር ስለ አስፈለገው ፣ አበሾቹ ወደ መረብ እንዳይዘልቁ ከአዲግራትና ከሳውሪያ ምሽግ ሠራዊቱ እሚዋጋ እየመሰለ በመውጣት የንጉሡ ጦር ባለበት በኩል በሰልፍ እንዲታይ ጄኔራል ባራቲዬሪ አዘዘ ። በዚህ



ምክንያት የካቲት 17 ቀን የታዘዘው ጦር በሰልፍ ለውጊያ አስመስሎ ወጥቶ ወደፊት ይጓዝ ጀመር ።[1]

የኢትዮጵያ ቃፊር ጠባቂዎች ፣ የኢጣልያኖችን በሰልፍ መምጣት በሩቅ ሲመለከቱ በፍጥነት ለንጉሠ ነገሥቱ አስታወቁ ። በዚህን ጊዜ ዐፄ ምኒልክ የኢፍራታውን ነጭ ደጃች ወልዴንና ያክስታቸውን ልጅ ደጃች በሻህ አቦዬን ፣ "ወደፊት ቀድማችሁ ሌሊቱን ተጠባበቁ ። እኔም ሊነጋ ሲል ጦሬን አስከትዬ እደርስባችኋለሁ" ብለው እነርሱ ወደፊት ቀድመው እንዲጠባበቁ አደረጉና እርሳቸው በማግሥቱ ሊነጋ ሲል ጦራቸውን ለውጊያ ግራና ቀኝ አሰልፈው ራሳቸው ከመካከል ሆነው ነጋሪታቸውን እያስጎሰሙ ወደፊት ተጓዙ ። ዳሩ ግን ፣ "የኢጣልያ ጦር ያጼ ምኒልክን ንቅናቄ ባየ ጊዜ ፣ በሰልፍ እንደወጣ ምንም ሳይታኩስ ተመልሶ በማግሥቱ እምሽጉ ገባ" የሚለው ወሬ ላጼ ምኒልክ ስለመጣላቸው ፣ እርሳቸውም ሠራዊቱም አዘኑ ። ይኸን ዓይነቱን ወጣ ገባ የማለት ሰልፍ ኢጣልያኖች ደጋግመው ሠሩበት ። በዚያን ጊዜ የኢትዮጵያ መኳንንትና ጦር ሠራዊት ፣ "ብቅ ይሉና ስንመጣባቸው እንደ ኤሊ እድንጋያቸው ውስጥ እየገቡ ይሸሸጋሉ ፤ እልፍ ስንል ደግሞ ብቅ ይላሉ ምን ይሻላል" እያሉ በብስጭት እጉረመረሙ ። ከዚያ በኋላ የሚያደርጉት ቢያጡ የጦር አለቆች ተሰብስበው ፣ "እዚሁ እያለንበት እንደርና ነገ በጧት ሔደን እምሽጋቸው ድረስ እንግጠማቸው" ብለው ተማከሩ ። የነርሱንም ምክር ንጉሠ ነገሥቱ በእሺታ አጸደቁት ።

በዚህ ምክር ሁሉም ተስማምቶ ከጨረሰ በኋላ ፣ ከዚህ ቀደም እንዳመለከትነው ራስ መንገሻ ዮሐንስ ወደፊት ቀድመው በሌላ ክፍል ይጠባበቁ ስለነበረ ፣ የዚህን የምክር ውሳኔ በሰሙ ጊዜ በጦራቸው ታጅበው በፈረስ ሆነው በግሥጋሤ መጥተው ፣ "ጃንሆይ ጉድባ ጎድቦ ምሽግ መሽጎ በተቀመጠ ጠላት ላይ በኃይል ብንገባ ሠራዊታችንን ከማስጨረስ በቀር ምንም ጥቅም አናገኝም ። ዐፄ ዮሐንስ ያ ሁሉ ጦራቸው መተማ ሔዶ ያለቀው በዕንጨት እተመሸገው ምሽግ ገብቶ አይደለ ምን? ስለዚህ ከድንጋይ እተመሸገው ምሽግ ይኸን ሁሉ ጦር ልናስጨርስ አይገባምና እኔ በዚህ አልስማማበትም" ብለው ተናገሩ ። ሁሉም የርሳቸውን ምክር ልብ አድርጎ ተገንዘበው ። ዐፄ ምኒልክም "እንግዲህ ወዲያ ኢጣልያኖች በሙሉ መጥተው መታኮሳቸውን ሳላይ ጦሬን ሁለተኛ አሰልፌ አልነግም" ብለው እየተበሳጩ ወደ ድንኳናቸው ተመለሱ ።[2] ሁለቱም ባላጋራዎች በዚህ መካከል የስንቁ

---

1 Memoire d' Afrique .. Chap. XXIX

2 ታሪክ ዘመን ዘዳግማዊ ምኒልክ ፣ ምዕ. 63 Italia ed Etiopia .. Conti - Rossini, PP. 300-315.

ነገር ከሥጋት ላይ ተጊቸዋል ። በኢጣልያኖች በኩል ለመብል የሚሆን ሥጋም አልቆ የጭነት በቅሎአቸውን እያረዱ የበሉና የሚበላ ዳቦ ለማግኘት ልብሳቸውን ላገር ተወላጅ ወታደር የሸጡ የኢጣልያ ወታደሮች አሉ ።[1]

እቴጌ ጣይቱም ፣ ራሶቹም ፣ ሹማምንቱም ፣ ወታደሩም በዚህ ነገር በጣም እያዘኑ ምን ማድረግ እንደሚሻል በሚወያዩበት ጊዜ ፣ እቴጌ ጣይቱ ፣ ደጃች በሻህ አቦዬን ጠርተው ፣ "ወንድሜ ሆይ ምን ይመስልሃል ይኸውና ጦራችንን ሁለት ጊዜ እያሰለፍን እየወጣን ሁለት ጊዜም ምንም ሳናደርግ ተመለስን ። ይኸም የእግዚአብሔር ፈቃድ ባለመሆኑ አዝኛለሁ" ብለው አማከሩዋቸው ። ደጃች በሻህም ፣ "ጦርነት የሚጀመረው ድንገት ሳይታሰብ ነው ። በጦርነት የሚሞቱትም ገና እህል ውሃቸው ባያልቅ ነው ። ይልቅስ ወደፊት ለሚሞቱት ይዘኑ እንጂ በሌላው ነገር አይዘኑ" ብለው መለሱላቸው ። በኋላም የዓድዋ ውጊያ ለት ደጃች በሻህ አቦዬ በጦርነቱ ላይ ስለሞቱ እቴጌ ይኸንን ንግግራቸውን አስታውሰው አዘኑላቸው ።[2]

በዚህ በየካቲት ወር ፣ የኢጣልያና የኢትዮጵያ ጦር አለቆች አንድ ዓይነት የስንቅ ችግር በነበረባቸው ጊዜ ሁለቱ ወገኖች አሳባቸው አልፈጸም ቢላቸውም ፣ በብዙ ችግር በብዙ ውይይትና ዘዴ ፈጠራ አንዱ ሌላውን ወደሚያሸንፍበት ምቹ ሥፍራ ስቦ ለመዋጋትና ለማሸነፍ ሲጣጣር ሰነበተ ። በዚሁ መሠረት ባራቲዬሪ ፣ "በየጊዜው ከምሽግ ውስጥ እንደሚዋጋ ጦር ብቅ እያላችሁ ለኢትዮጵያ ጦር በሰልፍ እየታያችሁ ሲመጡባችሁ ደግሞ ወደ ምሽጋችሁ ተመለሱ" ማለቱ ለጦርነት ሲል ፣ ቤት ንብረቱን ለቆ ከወጣ አምስት ወር ያለፈው የኢትዮጵያ ጦር በንዴት የተመለከተውን ጦር ተከታትሎ እስከ ምሽጉ ድረስ ሔዶ ሲዋጋ የመጣውን ጦር ምሽጋችንን ከለላ አድርገን በመድፍና በመትረየስ በጠመንጃም ፈጅተን በቀላሉ ድል እናደርጋለን በማለት ነው ። ነገር ግን ፣ የንጉሡን ብልሃት እነራስ መንገሻም እነራስ ስብሐትም በትክክል ስለሚያውቁት ፣ ወደ ምሽግ ተሔዶ ጦርነቱ እንዳይደረግ በጥብቅ ማሳሰባቸውን ተመልክተናል ። ንጉሠ ነገሥቱም እነራስ መኰንንም ቢሆን የምሽግ ጦር አስቸጋሪ መሆኑን እንደማይስቱት የታወቀ ነው ።

ስለዚህ ፣ ብዙ ቀን በመፋጠጥ ጊዜው ካለፈ በኋላ ፣ ዐፄ ምኒልክና ሹማምንቶቻቸው ደግሞ የኢጣልያ ጦር ልብ አግኝቶ ምሽጉን ለቆ

1 Gli Italiani in Africa Orientale, A. Del Boca, PP. 640-641.
2 ታሪክ ዘመን ዘዳግማዊ ምኒልክ ፣ ገጽ 258



ወደ ውጭ እንዲወጣላቸው በበኩላቸው ልዩ ልዩ የመሳቢያና የማታለያ ወሬ ይፈጥሩ ጀመር ። ከዚህም አንደኛው የኢጣልያ ጦር የልብ ልብ ሰጥቶት ወጥቶ እንዲዋጋ ፣ "የኢትዮጵያ ወታደር ስንቅ አልቆበት ለዘረፋ በያገሩ ተበትኗል ። ይበልጡም በያገሩ ተመልሶ ገብቷል ። እነራስ አሉላም ሞተዋል ። ወይም ከድተዋል ። ዐፄ ምኒልክ ታመዋል" እያሉ በውትወ ያስወሩ ጀመር ። ባንድ ወገን ደግሞ እነ ንጉሥ ተክለ ሃይማኖት ፣ እነራስ መኰንን ፣ እነራስ ሚካኤል ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር እየተጣሉ ፣ "ጦርነቱን ብትጀምር ቶሎን ወደናንተ እንገባለን" እያሉ ቢነግሯቸው ለጣልያኖች አዛዥ እስከ መጻፍ መድረሳቸውን ጸሐፊ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴና ነጋድራስ አፈወርቅ ያረጋግጣሉ ።[1]

1 ታሪክ ዘመን ዘዳግማዊ ምኒልክ . . . ገጽ 258 ፣ ዳግማዊ ዐፄ ምኒልክ ፣ ገጽ 32-33



ራስ ወሌ ብጡል ከልጃቸው ከደጃዝማች ዓመዴ ጋር
ከካርሎ እናቶሬ መጽሐፍ



ራስ መንገሻ ዮሐንስ በዓድዋ ዘመቻ ጊዜ
ከኤሪትሪያ አልጋሳቱ



በጦርነት ሰዓት የኢጣልያኖችን ጐራ በስውር ለቀው ወደወገናቸው ወደ ዓፄ ምኒልክ ጦር መጥተው የተደባለቁት ራስ ስብሐት

# ምዕራፍ ሠላሳ አምስት

## የኢጣልያኖች ተታይላነትና የጄኔራል ላቦርሚላ ደብዳቤዎች

ከዚህ በፊት እንዳልነው ፣ ፈረንጆች ከቆዳ ቀለማቸው የበለጠ በሥልጣኔያቸው ስለሚመኩ ፣ ባልሠለጠነው በእስያና በደቡብ አሜሪካ ፣ ይልቁንም ከመልኩ መጥቆር ጋር በሥልጣኔ በጣም ወደኋላ ቀር በሆነው በአፍሪካ ላይ ከጥላቻ ጋር የተደባለቀ ንቀት መኖሩ በየጽሑፉ ላይ ይነበባል ። ናቂዎቹ ኢጣልያኖች የኢትዮጵያን ተወላጆች ሁሉ በጠቅላላው አረመኔዎች እያሉ መጥራትን ያዘወትራሉ ።

ወደ ቀይ ባሕር ጠረፍ ኢትዮጵያን ቅኝ አገር ለማድረግ የሚመጡት የኢጣልያ የሲቪልና የጦር ሹማምንት ከንቀት የተነሣ ፣ በቀላሉ ያለ ምኒልክን ጦር አሸንፈው ለኢጣልያ ቅኝ አገር አውርሰው በመመለስ የሹመት ደረጃና ኒሻን ለመሸለም ቁና ጉጉት አላቸው ። ወዲያ ምኒልክ ለእርቅ እያስመሰለ ይመላለስ የነበረው ማዦር ቶማሶ ሳልሳ የሚባለው ፣ "ቁጥሩ ትንሽ የሆነው ወታደራችን ብዙውን የጠላትን ኃይል ለማሸነፍ መቻሉ አጠራጣሪ አይደለም ..." በማለት እርግጠኛ ሆኗል ።[1]

ራሱ ጠቅላይ አዛዡ ባራቲዬሪ ፣ ቀደም ሲል ለውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ለባሮን ብላን ባስተላለፈው መልእክት ፣ "ጄኔራል ናፒዬሩ ቴዎድሮስን ለማሸነፍ ከፈጀበት የወታደሮች ቁጥርና ጊዜ ባነሰ በምኒልክ ጦር ላይ ድል አድራጊነትን እቀዳጃለሁ" ብሎ ደንፍቶ ነበር ።[2] ከዚህም አያይዞ ከኢትዮጵያ ጦር አንጻር የኢጣልያን ተዋጊ ጦር በፖለቲካ መብሰሉን በወታደራዊ ሥነ ሥርዓት የሠለጠነ መሆኑን በመገምገም ለድል አድራጊነቱ አልተጠራጠረም ።

ሌላው ጄኔራል ማቲዮ አልበርቶኒ የሚባለው ፣ በዓድዋ ጦርነት ቀዝማ አጠገቡ ያሉት ደጃዝማች ፋንታ የሚባሉት የባንዳ ሹም ፣ በዚህ ጦርነት ጥንቃቄ ማድረግ እንደሚገባ ቢመክሩት ፣ "አበሾች

---

1 Il Generale Tomaso Salsa, E. Canevarie. G. Comisso, PP. 268-269.

2 Gli Italiani in Africa... Del Boca, P. 560.

ንና ሲያዩን ነው የሚሸሹት" ሲል መለሰላቸው ። የርሱም ጓደኛ ጄኔራል አሪሞንዲ ዝቤፔ ጄኔራል ባራቲዬሪ በመጨረሻ በቶሎ ጦርነቱን ካለመጀመር የሚያደርገውን ጥንቃቄ በመንቀፍ ምክንያት እያበዛ ነገ ተነገ ወዲያ እያለ ጊዜ በማራዘሙ እየተበሳጨ ፣ "አሁን ጠላትን ልቡ እስኪጠፋ እያደኑ ማባረር ነው" ያለውን እንጀሎ ደል ቦካ መዝገቦት ይገኛል ።[1]

ከንዚህ የበለጠ ደግሞ ፣ የንዚህ ጄኔራሎች ጓደኛ ጄኔራል ጂቶሪዮ ኢማኑኤል ዳቦርሚዳ ባንድ ወገን ካፄ ምኒልክ ሠፈር በዘዴ እያሉ የኢጣልያን ጦር ከምሽጉ ለማስወጣት የተንዛዛውን ሐሰተኛ ወሬ በመተማመን ፣ ወዲያውም እንደ ጓደኞቹ ጄኔራሎች የኢትዮጵያን ጦር በመናቅ ፣ የኢትዮጵያን የወታደር ድርጅት በቀላሉ አፈራርሶ የአሳዳውንና የመቀሌውን የውርደት ብድር ለመመለስና በክብርና በድል አድራጊነት ወደ አገሩ ለመመለስ እርግጠኛ እንደነበረ ከዓድዋ ጦርነት ከሐያ ቀን በፊት ወደ ኢጣልያ አገር ለባለቤቱ የጻፈው ከዚህ ቀጥሎ ያለው ደብዳቤ ያስረዳል ።

> እንትጮ የካቲት 10 ቀን 1896 (የካቲት 3/1888) የልጆቻችንን ደብዳቤዎች ተቀበልኩ ። ግልጽ በሆነው ፍቅራቸው ልቤ ተነክቷል ። ካንድ ወር በኋላ የምንመለስ(ወዳገራችን) አይመስለኝም ። በአፍሪካ ነገሩ ሁሉ እየተጓተተ መርዘም አለበት ። ጠላት ወደፊት ከገፋ በኋላ ወደኋላ መሸሽ ብቻ ነው ። * እኛም ከአስገዶች ከአዲግራት ወደ እንትጮ አልፍ ብለናል ። ከአስገዶች ስድስት ኪሎ ሜትር ራቅ ብሎ የጠላት ጦር ይታያል ። የቀረው ወደኋላ ያለው በጋራ ተሸፍኗል ። እኔ እንደ ማስበው በድንገት እዚያ ጥሰን ብንወጋው የሚሸሽና በትንሽ ወታደሮች መሥዋዕትነት ከፍ ያለ ፍሬ (የድል) የሚገኝ ይመስለኛል ።
>
> የኛ ወታደሮች ፣ የውጊያ እምርት እያላቸው እንዲያ (ሐበሾቹ) ግን ፣ ሰላዮቻችን እንደሚሉት ወደቤታቸው መመለስን እንጂ ፣ በጦርነቱ እምነት የላቸውም ። ነገር ግን የዕርቅ ድርድር ተጀምሯል ። ** እኔ ለዕርቁ ፍሬነት እምነት የለኝም ። ንጉሡ (ምኒልክ) በረኸኛው ጦርነቱን አዘጋጅቶ 80,000 ወታደር ከአሰከተተና የግቀቱን ሀብት ከፈጀ በኋላ ምንም እንኳን ከብሩ የኛ ቢሆን ፣ በእምባ አላጌና በመቀሌ ከቀናው በኋላ እኛ የምናቀርበውን ውል ተቀብሎ ወደቤቱ ለመመለስ ይችል ይሆን ። ኢጣልያስ ብትሆን ከነርሱ የተሻለ በዓለም የማይገኘውን 20,000 የጦር ወታደሮቿን ወደዚህ በመላክ ከፍ ያለ መሥዋዕት ከአደረገች ወዲህ ከአንድ አረመኔ ሕዝብ የሚቀርብላትን የውል እሳብ ተመቀበል ትቀርሳለችን! የዕርቁ ድርድር ጉዳይ እየተራዘመ ሲሔድ

1 Gli Italiani in Africa ..., PP. 640-642.

* መረብን አልፎ ወመዝመት ታስቦ በወቅቱ አሎት የቀረውን ለማስታወስ ይመስላል ።

** ማጆር ሳሊሳ ከራስ መኮንን ጋር ያደረገውን ሙግት ነው ።



> የጠላትን ውጊታ እያዳበበት ይሔዳል እንጂ ። ቢሆንም ለኛ አጥፊ ዕርቅ ሊያደርሱብን አይችሉም ። እኔ ግን ጠላት ወደኋላ የተመለሰ እንደሆነ ያጋጠመኝን መልካም ዕድል አጣለሁ* ምክንያቱም ወደኋላ ሲያፈገፍግ ኃይላችንን ይዘን እርሱን እየተከታተልን ፈልገን ለመውጋት የበጎቄ ነገር (ችግሩ) ይከለክለናል ።[1]

ይኸው ለውጊያና ለገበዱ በዚህም ለመኸምና ለመሸለም ጉጉት ያደረበት ጄኔራል ፣ ከዚያ ወዲህ የዓድዋ ጦርነት ሊደረግ ስምንት ቀን ሲቀረው በጻፈው ሌላ ደብዳቤ ላይ ፤

> የኔ ኳና እትዋሬ ። እዚህ ያለተገነቃ የሚሆን ነገር የለም ። ሁሉ ቱም ባላጋራዎች በጣም ጠንቃቃ ሆነዋል ። . . . በግልጽ ሜዳ በዝዕድ መዋጋት አይፈልጉም . . . እበሾች መዋጋት ወይም መመለስ እንዳ ለባቸው በኛ በኩል የታመነ ነው ። ምክንያቱም ጠላት 80,000 ተዋጊ ጦር ሲኖረው ከሴትና ከልጅ ጋር በድምሩ 150,000 ተቀላቢ ስለሆነ እንዚህን ለመቀለብ ያለበት አገር እሁሉ ስላለቀ አይችሉም ። ከምሽ ጋችን መጥቶ ለመውጋት አይደፍሩንም ። ስለዚህ በመጭው ጊዜ ወደ ኋላው ይመለሳል ብለን እንጠባበቃለን ። በዚያን ጊዜ በትግሬ የፈተደንን ለማድረግ እንችላለን ። ተመልሰው ተዘጋጅተው ለመምጣት ብዙ ዓመት ይፈጅባቸዋል ። ዋናው ከሰበኛ አገር ተዋጊ የሆነው የትግሬ ሕዝብ ከኛ ጋር ስለሚሆን ምንም ማድረግ አይችሉም ። . . . መኖም ባለፈው ከደረሰው እድራጐት ያላገና የመቀሌ ውድቀት በኋላ ዕርቅ ማድረግ ለኛ አዋራጅ ነው ። . . . ከኢጣልያ አገር የጦሩ እርዳታ ከደረሰ በኋላ ባራቲዬሪ ጉልበቱን ተማምኖ ውጊያ የሽመረ እንደሆነ መፍ ትሔው በመጋቢት ላይ ይለያል ። ** ስለዚህ ወደ ኢጣልያ አገር መመ ለሳችን በበጋው ነው ማለት ነው . . . ትናንት የሁለት ባታሊዮን ጦር ይዤ ለምርመራ በወጣሁ ጊዜ በወታደሮቻችን ፊት ላይ ይታይ የነበረው ደስታ ይገርምሃል ። ሁሉም ወደፊት ገሥግሠው መታኮስ ይፈልጋሉ ።[2]

በነዚህ ሁለት ደብዳቤዎች ፣ ይህ የኢጣልያ ጄኔራል የራሱን ወታደሮች "በዓለም የማይገኙትን" ሲል ካገሩ ያልወጣ ወይም በገባብ ያል በሰለ ፣ ዓለምን የማያውቅ በዓለም ያሉትን የጀርመንን ፣ የጃፓንን ፣ የቱርክን የሌሎችንም አገሮች ወታደሮች ዝግጅነት የማያውቅ በምኝነት የራሱን ወገን ብቻ የሚያጋንን የዋህ ጄኔራል መሆኑን ያሳያል ። በዚህም ላይ ለኢትዮጵያ ሕዝብ ደግሞ አረመኔ የሚል ሥያሜ እስታቅ ፎታል ። አረመኔ በራሱ ግዛት ሳይቆጠብ የሌላውን አገር ካልገዛሁ

* ተዋግቶ ዝግጅነትን አላይቶ የመሸሸም ፣ የመሸለም ዕድል ማለት ነው ።

1 Lettere e Diari ..., F Lemmi, PP. 82-83.

** እውነትም የዓድዋ ጦርነት የተደረገው እ.ኤ.አ. መጋቢት 1 ቀን ስለሆነ ትንቢቱ ደረሰለታል ።

2 Lettere e Diari ..., F. Lemmi, PP. 83-84

ብሎ የንጉሡን ደም የሚያፈስ ነው ወይስ የራሱን ነጻነት የሚከላከል ? በመቀሌ ተከበው በወሃ ጥምና በረኃብ ሊያልቁ የነበሩትን ሸኘ ስተቶ በነጻ መልቀቅ የጠላቱን ሬሳ እስከሥሙ በደንበኛ ቦታ ማስቀበር ፣ ይኽ ሁሉ ያረመኔ ሥራ አልነበረም ። ዳሩ ግን ፣ ይኽን ሁሉ የጦሩ አለቆችና የፖለቲካ ባለሥልጣኖቹ ከፍርሃት ቆጥረውታል ።

ዳቦርሚዳ ፣ እሸናፊነቱን መቶ በመቶ በማመን ፣ "ጠላት ወደኋላ የሸሸ እንደሆነ ለመከታተል ስንቅ ስለሚቸግረን ፣ ያጋጠመኝን ዕድል እጣለሁ . . . እንደዚሁም ከአገሬ ለውጊያ መጥቼ ጠላት የሸሸ እንደሆነ እሸንፌ በዚሁ የማገኘው ክብርና ዝና ይቀርብኛል . . . ጠላት ስንቅ አልቆበት ወደቤቱ (አዲስ አበባ) ሲመለስ ፣ በመላው ትግሬ የፈቀድ ነውን እናደርጋለን" ሲል ፣ በእርግጥ ኢትዮጵያ በዚህ ጊዜ ያላትን ድርጅት የማያውቅ ካለፉት ከአላጌና ከመቀሌ የውጊያ ውጤቶች ለመማር ያልፈለገ በጠቅላላው አመዛዛኝ አእምሮ የሌለው ምኞትና ግትርነት ያጠቃው ተራ የጦር አለቃ ነው ማለት ይቻላል ።

በዚህ ላይ ደግሞ ፣ ጦርነቱ ይቅርብን የሚል ሕዝባዊ ድምፅ እንዳ ይቀሰቀስ የጠቅላይ ሚኒስትሩ ሮማም እሥመራና ምጥዋም ያሉት የሲቪልና የጦር ሹማምንቶች በኢትዮጵያ ያለውን ደንበኛ የመከላከያ ሁኔታ እየደበቁ በአምባላጌና በመቀሌ የደረሰውንም እያወላገዱ በከንቱ የኢትዮጵያን የመከላከል ሁኔታ እያራከሱ ፣ የነርሱን ጀብዱ እያጋነኑ በመጻፍ ሐቀኛውንም ጋዜጣ ጸሐፊ እያባረሩ ፣ ብዙውን ሁኔታ ከተዋጊው ወታደርና ጄኔራል ለመደበቅ መሞከራቸው ግልጽ ነው ።

በጠቅላላ ፣ ኢጣልያኖቹን በጄኔራሎቻቸው መልክና ጠባይ ልን ወስዳቸው እንችልም ። በመካከላቸው በኢጣልያ አገርና በሮማ ታላላቅ አስተዋዮች ፣ ብልሆች ምራል ያላቸው ደግነትም ርኅራኄም የሞላባቸው ይገኛሉ ። በዚህ ምክንያት ፣ በምክር ቤት ውስጥ ሳይቀር ከራሲፒና ወገናቹ ኢትዮጵያውያን አረመኔዎች ናቸው ፣ እናገዛን ልናሠለጥናቸው ይገባል እያሉ ሲደነፉ ፣ ሌሎች በተለይ የግራ ክፍሎች እስከዛሬ በነጻነት የቆዩትውን አገር በኃይል ወርሮ በቅኝ እንገዛ ልያዝ ማለት ወንጀልም እብደትም ነው እያሉ ሽንጣቸውን ገትረው የሚሟገቱ ሞልተዋል ። ከነዚህም ውስጥ ኮስታ እንድሬያ ይገኛል ። ይኽም እማካሪ በአምባላጌ ለወደቁት የክብር ሰላምታ ይስጥ በተባለበት ጊዜ ፣ "በፖለቲካ ብልሹነት ያላግባብ ለወደቁት ኢጣልያኖች ክብር ከመስጠቱ ጋር ያገራቸውን ነጻነት ሲከላከሉ ለወደቁት አበሾችና የሸዋ ተወላጆች የክብር ሰላምታ መስጠት ይገባል" በማለቱ



በምክር ቤቱ አጭር ሁካታ ተፈጥሮ ነበር ። ከርሱም ጋር ይኸን በመሰለው አሳብ የተባበሩትን ኢምብሪያኒ ማቲዎ ፣ ኡሊስ ባርቢዬሪ ፣ ጋብርኤል ሮዛ ፣ ናፖሊዎን ኮላጆያኒ የሚባሉትን ስማቸውን መጥቀስ ተገቢ ይመስለኛል ።[1]

1 Gli Italiani in Africa .. PP. 287 - 289; La Prima Guerra D' Africa, R. Battaglia, PP. 242 - 238.

# ምዕራፍ ሠላሳ ስድስት

## የመጨረሻው የኢጣሊያኖች ተስፋ ልጅ ጉግሣ ዳርጌ

ዳግማዊ ምኒልክ ፡ የኢትዮጵያን መሳፍንትና መኳንንት ፡ ሹማምንቱንም ፡ ባላባቱንም ጠቅላላውን ተዋጊ ጦር በክተት ዐዋጅ ቀስቅሰው ለዚህ ጦርነት ከአዲስ አበባ ከተነሡ ገምሮ ከአዳዋ እስከ መቀሌ ከድል ወደ ድል እየተራመዱ ፡ እንደልቡ ፈንጭቶ እስከ አምባላጌ የደረሰውን የኢጣልያን ጦር እየጠረጉ ወደ ዓድዋ አካባቢ ነድተውታል ። ወደ ኢጣልያኖች በውድም ፡ በግድም ተጠግቶ የወረራ መግፊያ የሆነውን ኢትዮጵያዊ መልሰው ለእናት አገሩ እንዲሰለፍ ለማድረግ በዓዋጅና በመልክት እየጋበዙ አስገብተውታል ። በሌላውም ረገድ ኢትዮ ጵያ ካሳለፈችው የጦርነትና የዕልቂት ዘመን ዐርፋ ሰላምና ጸጥታ እን ድታገኝ ለጣልያኖቹ ባለሥልጣናች የሰላም እጃቸውን ከመዘርጋት ሳያቋርጡ ፡ በማናቸውም ረገድ በሚያደርጉት ፖለቲካዊና ወታደራዊ ተግባር እነሱ ቢያምኑም ፡ ቢክዱም የኢጣልያን ጉራ እያሳከሙበት ሔደዋል ። ሰላምን የሚፈልጉት ከኃይል ተጽዕኖ ጋር ጦርነቱንም የሚቀጥሉት የሰላምን መንገድ በመከተል ስለሆነ ፡ ኢጣልያኖቹ ከተቀር ሕዝብ እንደዚህ ያለ ያልጠበቁት ከፉ ጠመዝማዛ የፖለቲካና የጦርነት መዘዝ ገጥሟቸዋል ። የተማመኑባቸው ራስ ሰብሐትና ደጃች ሐጎስ ተፈራ ፡ ኢጣልያንን ከድተው ወዳጌ ምኒልክ መደ ረብ ፡ በሚቀጥለው ምዕራፍ እንደምናነበው ፡ በእውነት የመሐመድ አን ፋሪ በነአዋቹ ወልደ ጻድቅ ተመትቶ መሸነፍ ፡ የመሳፍንቱ በምኒ ልክ የሥልጣን ጥላ ሥር ተባብሮ ለጦርነት ባንድ አገር መቆም ፡ ለኢጣልያ የተደጋገመ ታላቅ በትርና የራስ ምታት ሆነባት ።

ነገር ግን ፡ ከመሐመድ አንፋሪ ከዳት በቀር ገንዘቡም ፡ ስጦታው ውም ተበትኖ ፡ የወዳጅነት ሰብከቱና ማስፈራሪያውም በየወቅቱ ተፈራ ርቆ ለክዳት የሚነቃነቅ መስፍን ባገር ውስጥ ስለጠፋ ፡ ለምኒልክ የዙ ፋን ባላንጣ ሆኖ ራሱ ከድቶ ሌሎቹን የሚያስክዳ ቢቸግራቸው ከውጭ አገር ይፈላለጉ ገመር ። በዚህ ምክንያት ፡ ቀደም አድርገው ዐጼ ምኒ ልክ እንደሊጋያቸው በነበረው በስዊሱ ተወላጅ በኢንጂነር አልፍሬድ ኢልግ አማካይነት የራስ ዳርጌን ልጅ ጉግሣን ከኩተማና ከአፈ ወርቅ (በኋላ ነጋድራስ አፈወርቅ) ጋር ለትምህርት ወደ ስዊስ አገር ልከዋ ቸው ፡ ምስቱም ወጣቶች በስዊስ አገር በኳኛተል ኮሌጅ ይማሩ ነበር ።

ጠቅላይ ሚኒስትሩ ፍራንቼስኮ ክሪስፒና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ብላን ካርሎ አልበርቶ የሚያደርጉት ቢያጡ ፤ "ጉግሣ የራስ ዳርጌ ልጅ ስለሆኑ ዳርጌም የማህል ሥላሴ ልጅ በመሆናቸው ፤ እንደ ምኒልክ ለዙፋኑ ቀራቢ ስለሆነ ጉግሣን በማባበልም ፤ በማስገደድም ከኔኛተል ኮሌጅ እናተለን ወደ ጀኔራል ባራቲዬሪ ብንልከው ፤ ጀኔራሉ ይኸን ይዞ ከምኒልክ ብዙ ሰው ለማስከዳት ይችላል " የሚል የሚያስፍርና ወራዳ የሆነ ከንቱ ተስፋ አደረባቸው ።

ስለዚህ ፤ ጉግሣን ከባዶቹ ከኩተማና ከአፈወርቅ ጋር (ምናልባት ኢጣልያንኛ በሚያውቀው በአፈወርቅ በኩል) አባብለው ወደ ኢጣሊያ ጠረፍ ጠጋ ሲል እ. ኤ. አ. በታኅሣሥ ወር በ1895 ዓ.ም. በግዱታ ይዘው ወደ ሮማ ለማምጣት እንደ ወሰኑ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ብላን ለጀኔራል ባራቲዬሪ ከዚህ ቀጥሎ ያለውን ቴሌግራም አስተላለፉለት ።

> የልበኛው መስፍን ጉግሣ በታኅሣሥ ወር በመጀመሪያዎቹ ቀኖች ሮማ ይገባል ። ከሁሉንትም መስፍኑን በምኒልክ ላይ መሣሪያ አድርጎ ለመጠቀም ይመኝ እንደሆነ አባብለን (አግባብተን) ወደ ምጥዋ ልከን በሥልጣናችን ሥር እንዲሆን እናደርጋለን ።

ጀኔራሉ አሳቡን ከተቀበለው በኋላ ፤ ጉግሣንና ባዶቹን ከስዊስ ነጥቀው ወደ ሮማ አስመጧቸው ። ንጉቲያው ማባበልና ማጭበርበር አሰቡት ። ከዚህ በኋላ ሮማ ምንም ያህል ውለው ሳያድሩ ፤ በመርከብ ወደ ምጥዋ ተልከው እንደ ደረሱ ፤ ከዚያ በእንክብካቤ ጀኔራሉ ወዳለበት ወደ እዳጋ ሐሙስ አደረሱት ። ጀኔራሉም ከአንገት በላይ የሆነ አክብሮት እያሳየ ጉግሣን እንጋገረው ። ሴሎቹም ሹማምንቶች አክብሮት እንዲያሳዩት አደረገ ።

በዚህ ጊዜ ፤ ይኸን የመንገሥ እምርት የሌለውን ወጣትና ዐይን አፋር ተማሪ ፡ ከስዊስ አገር አታለውና አስገድደው ወደ ሮማ ፤ ከሮማ ወደ እዳጋ ሐሙስ መላካቸውን የሰማና "" ከምኒልክ ብዙ መሳፍንት ያስከዳልናል " በሚሉ ምኞት ልባዊ ያልሆነ የማታለል አክብሮት ማድረጋቸውን የተመለከተ ሁሉ ማተባቸው ‹መስፍኑ ጉግሣም ከጎ ምኒልክ ሠፈር እንድም ሰው ሊያንቀሳቅሳቸው አልቻሉም ። ተስፋ ሲቆርጡ አክባብረው ፤ እንክባክበው የመሣሪያንቱ ጉዳይ ስለሳተ እመናጭተው ወደ ነበረበት ወደ ስዊስ መለሱት ።

ራሱ ጀኔራል ባራቲዬሪ ፤ ከዓድዋ ጦርነት በኋላ በግዞት እንዲሆ ንበቱ በዕረፍቱ ጊዜ በጻፈው መጽሐፍ ስለዚህ ጉዳይ ያወፈረውን ከዚህ እንደሚከተለው እንመልከት ።



> ... ከሮማ ወደ ሠፈራችን ስለ ተላከው የሸዋ መስፍን ትንሽ እናገራለሁ ። ... የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ባሮን ብላን ኢትዮጵያዊው መስፍን ጉግሣ ሊጠቅም ይችላል ብሎ በቴሌግራም ጠየቀኝ ። ይህ መስፍን የራስ ዳርጌ ልጅ ሲሆን ፡ ለንጉሡ ነገሥቱ ለምኒልክ ያጎት ልጅ ነው ። ... ስለዚህ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ለጠየቀኝ አወን ብዬ መለስሁ ። ስለዚህ ጉግሣ ከሁለት ባዶቹ ጋር ምጥዋ ከዚያም አዲግራት ደረሰ ። ለርሱና ለባዶቹ ማናቸውም አክብሮትና እስተያየት ተደረገላቸው ። በእዳጋ ሐሙስ ሠፈር ድንኳናቸው በዋናው ጦር ጠቅላይ እዛዥ ድንኳን አጠገብ ተተከለላቸው ። ነገር ግን ፤ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ በዚህ ጉዳይ ላይ ለመጠቀም የሠነዘረው ዓላማ ከመጠን ያለፈና የሳተ ነገር መሆኑ እርግጠኛ ነበር ።
>
> መስፍኑ ጉግሣ ፤ እንደ ሌሎቹ ሁሉ የምኒልክ ያጎት ልጅ በመሆኑ በሸዋ ሠፈር ምንም የመታወቅና የመሰማት ክብር ሊኖረው አልቻለም ። በመከበር ፈንታ እንዲያውም ከሸዋ በመራቁና ያውሮፓን ሥልጣኔና ልማድ በመውሰዱ ምናልባት ሳይናቅ አይቀርም ። እርሱም ትንሽ ወጣት የተዋቂነት መንፈሱ ያነሰ ፤ ግልፍ ፤ ዝምተኛ ፤ ሁኔታውና መንፈሱ የቀዘቀዘ ፤ በባልያናቹ ሠፈር በመገኘቱ የደነገጠና የበረገገ ነበር ። የሱ ጸሐፊ በትርጅ እውሮፓዊ የሆነ የባና ሐይቅ ተወላጅ (አፈወርቅ ዘብሔረ ወገ) ስለ ራሱም ስለ መስፍኑም ሲናገር ፤ ግሊያናችን እንደሚወዱና ለማገልገል ፈቃደኞች መሆናቸውን ደጋግሞ ይናገር ነበር ።* ነገር ግን ፤ በእዳጋ ሐሙስ በጥር ወር መጨረሻ ጉግሣ ሊስባቸው የሚችለው በንጉሡ ነገሥቱ ጦር ሠፈር ያሉት ወዳጆቹ እነማን መሆናቸውን ለማወቅ ተፈልጎ ቢጠየቅ ትንሽ አወላውሎ እንዳንድ ስም ሰጠ ። ላለመጸፍና ራሱን ላለመግለጽ እንደ ሐበሻ ልማድ ምክንያት እየፈጠረ ጊዜ ያራዝም ጀመር ። ... በማናቸውም ረገድ በጣሊያኖች ሠፈር መካከል ሆኖ ጠብና ልዩነት ለመፍጠር ከወይን እፋፋ ከጉግሣ ሌላ ማናቸውም ዓይነት ሹም ... ሊጠቅመን በቻለ ነበር ። ... ጉግሣም ምንም እንኳን ለሐበሻ መስፍንነቱ የሚገባውን ክብር ብናደርግለት ፤ እርሱ ግን ሐበሾቹን በማየት እዳጋ እንዳይደርስበት ማናቸውንም ምክንያት እየፈጠረ ከእዳጋ ሐሙስ ወደ አዲግራት ከዚያም ወደ ምጥዋ ተመለሰ ። 1

የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩና ጠቅላይ ሚኒስትሩ ከባራቲዬሪ ጋር ውስጡን ተመሣጥረው ጉግሣን ከስዊስ ወደ ሮማ ከዚያም ወደ ምጥዋ ለመላክ በሚዘጋጁበት ሰዓት የኢትዮጵያን መሳፍንት ለመከፋፈል የተመደቡት ፤ በኢትዮጵያ የነበሩትና በኋላ በጦርነቱ ጊዜ ግ ካገር እንዲወጡ የተደረጉት ፤ እንቺቫሬ ኔራቢኒ ምንም ካገር ቢወጡ

---

* በዚህ የባራቲዬሪ ማስታወሻ ላይ አፈወርቅ ገብረየሱስ ከሰባት ዓመታት በፊት የመጣሊያን ፤ ውል ኪንዜብ ላይ እንቁላል አደገኛ መሆኑን ለደጃች መኩንን ገልጸውላቸው ሊሉ አሁን በዓድዋ ጦርነት ዋዜማ ምን ለመጣቸው ንገሰበ ወይስ ጋይልኦ እዶታወቅም ።

1 Memoire d' Afrique, Gen. Baratieri, PP. 354-355, I Russi In Etiopia, 2vol. Carlo Zaghi, P. 245

በጉን ወደ የመሳፍንቱ እየተሳሳኩ ለማሸፈት ያሳቸውን ምኞት በፍጹም ተስፋ ቆርጠው አልተውቱም ።

ከዚህ በፊት ፤ በሐረርና በአካባቢው ራስ መኰንንን እንግዛ ከምኒልክ ለመለየት ፈትና ያልተሳካለት ሐኪሙ ቼዛሬ ኔራቢኒ የኢጣልያ መንግሥት በምኒልክ ፈንታ ጉግሣን ደጋግፎ ለማንገሥ ያሰውን ዓላማ አባትየው ራስ ዳርጌ በውቀው ተደስተው በጉዳዩ እንዲተባበሩ ደብዳቤ ልኮላቸው ናሯል ። ደብዳቤውን የላከው ከአደን መሆን አለበት ። የርሱ ደብዳቤ ከሮማ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር መዝገብ ቤት ተፈልጎ ሊገኝ አልቻለም ። የራስ ዳርጌ መልስ ግን ፤ ቃሉ ከዚህ እንደሚከተለው ነው ።

> የተላከ ከራስ ዳርጌ ይድረስ ከሐኪም ኔራዚኒ እንዴት አለህ እኔ እግዚአብሔር ይመስገን ደህና ነኝ ። ወረቀትህም ደረሰልኝ ። እኔ ከዚህ ቀደም አላውቅህም ነበር ። አሁን በወረቀትህ ነው ማወቄ ። ከዚህ ቀደም ደህን ያህል ቀን ሳላውቅህ መቅረቴ ምንኛ ተጉድቻለሁ ። አሁንም የልጄን የልጅ ጉግሣን ነገር ወደ ኢጣልያኖች መግባቱን የሳ ከህብኝን ሰማሁ ። ይኸማ ከሆነ መልካም ነው እንጂ ምንነገር አለ ። ያጤ ምኒልክን አልጋ መቀበል ነው እንጂ ። እኔም አባቱ አጼስ አበሣን አልጋውን ይገፍ ተቀምጫለሁ ። ምን የሚቸግር ነገር አለ ። ዳሩ ግን ፤ ያንተ ደብዳቤ ብቻ ነው እንጂ የመጣው የሌላ ደብዳቤ አልመጣም ። ይህ ነገር እስት ውሸት የሆነ እንደሆን አንተንም ኔራዚኒ የተባልከውን ናዚራ አባብ ባለ መርዝ ያስመስልሃል ። ኢጣልያኖችንም ጉልበት ቢያንሳቸው የሐበሻን ጉልበት የሌሰት ያስመስላቸዋል ። ያንተንም ሐኪምነት የመልካም ፤ የደግ የነበርከውን የውሸትና የቅጥ ፊት ሐኪም ያስመስልህ ይመስላል ። ዳሩ ግን ፤ ሐሰቱንም እውነቱንም የሚያውቅ መድኀኒት (እግዚአብሔር) ይመልከት ። በጥር ፳፩ ቀን ተጻፈ ባዲስ አበባ ከተማ በ፲ወ፰፻፹ወ፰ 1888 ዓመተ ምሕረት (ዝ ማኅተም በራስ ዳርጌ ርእሰ መኳንንት)

ራስ ዳርጌ ፤ ያጼ ምኒልክ አጎት ብቻ ሳይሆኑ ሁሉቱ ከልብ እንደ አባትና እንደ ልጅ የሚተማመኑ ናቸው ። ኔራቢኒ ጉግሣን ለማስከዳትና በርሱና በርሳቸው ለመጠቀም ያቀደው እሳብ በጣም ገርሟቸው በስጡት መልስ ፤ “ ናዚራ አባብ ባለመርዝ ፤ ውሸታምና ቀጣፊ ሐኪም ” እያሉ በመሳደብና በማፌዝ ቀልደውበታል ።

የምኒልክና የጣይቱ ጠንካራና የደረጀ መንግሥት ፤ ለጠቅላላው ሕዝብ ጥቅም የሆነ የተሻለ አስተዳደር በማሳየት ፤ ሁሉን እንደ ልማዱ በመያዝ በትዕግሥት ፤ በሰላም ፤ በቸርነትና በመልካም ሁኔታ ላይ ስለ ተመሠረተ ፤ በዚህም በሌላውም ጊዜ ቢሆን እንኳን ሕዝብ የማያውቀው ተግሪው ጉግሣ ቀርቶ ራሳቸው ትልቁና የተከበሩት አባቱ ራስ ዳርጌ ቢከዱና ወደ ኢጣልያ ቢዞሩ ፤ የምኒልክን መንግሥት የጠነከረ አቋምና የጦርነቱን ጉራ እምብዛም ሊያናጉት የሚችሉ አይመስልም ።



# ምዕራፍ ሠላሳ ሰባት

## የአውሳ ሡልጣንና—የመሐመድ አንፋሪ መሸነፍ

የኢጣልያ ሰላዮች ፥ በኢትዮጵያ በየአውራጃው ተሠራጭተው የየአካባቢው መሳፍንትና ባላባት ከንጉሠ ነገሥቱ ከዐፄ ምኒልክ እየሸፈቱ እንዲለዩ በስጦታም ፤ በማባበልም የሚያደርጉትን ጥረት በመቀጠል ወደ አውሳው ባላባት ወደ መሐመድ አንፋሪ ለስብከትና ካዐፄ ምኒልክ ለመለየት የተላከው ካፒቴን ሳልቫቶሬ ፔርሲኮ መሆኑን አመልክተናል ።

የአውሳ ባላባቶች ምንም እንኳን አካባቢያቸው ለተወሰነ ጊዜ የቱርኮችና የግብጾች ተጽዕኖ ቢደረግበትም ፤ ቱርኮችና ግብጾች ከተባረሩ ወዲህ እንደገና ከንጉሥ ሣህለ ሥላሴና ከሌሎች የሸዋ መሳፍንት ጋር ግንኙነታቸውን አጽንተው ይኖሩ ነበር ። በዚሁ መሠረት የአውሳው ባላባት መሐመድ አንፋሪ ለንጉሥ ምኒልክ ታዛዥም ፤ ወዳጅም ሆኖ ከአውሮፓ ፤ ከፈረንሳይም ከኢጣልያኖችም ፤ በአሰብ በኩል ለንጉሥ ምኒልክ የሚመጣውን የጦር መሣሪያና ዕቃ እየተቀበለ ወደም ለሚያደርሱት ሸኚ እየሰጠ ፤ ወደ አንኮበር ለአዛዥ ወልደ ጻድቅ በመላክ መልካም ግንኙነቱን ጠብቆ ይኖር ነበር ። መንሲንጀር ባሻ የሚባለው በአውሳ በኩል በዐፄ ዮሐንስ ላይ የጦር ግንባር ለመክፈት እንደ እ.ኤ.አ. 1875 ዓ.ም. ሲተላለፍ ፤ የአንፋሪ ሰዎች በገደሉት ጊዜ ያስገፈፈውን አንዳንድ የጦር መሣሪያና ዕቃ ወደ ንጉሥ ምኒልክ በመላክ በማናቸውም ረገድ ታማኝነቱን እስከዚህ ድረስ አላጉደለም ነበር ።[1]

ዳግማዊ ምኒልክ ንጉሠ ነገሥት ከሆኑ ወዲህ ፤ በመጀመሪያው ጊዜ ይኸው መልካም ግንኙነት አላቋረጡም ነበር ። ነገር ግን ፤ ባለፈው እንዳነበብነው በውጫሌ ውል በ17ኛው አንቀጽ የተነሣ በንጉሠ ነገሥቱና በኢጣልያ መንግሥት መካከል ያለው ጠብ እየተባባሰ ሲሔድ እነኮንት አንቶኔሊ በአውሳ በኩል በሚተላለፉበት ጊዜ ከመሐመድ አንፋሪና ከአጣኞቹ ከአብዱራህማን ጋር መሣሪያና ሌሎች ስጦታዎችም በማድረግ ተወዳጁ ። እደያር ሁሉቱንም ከንጉሠ ነገሥቱ ሊለዩዋቸው ቻሉ ።

---

1 ታሪክ ዘመን ዳግማዊ ምኒልክ ፥ ገጽ 232

በመጨረሻ መሐመድ አንፍሬና አማቹ አብዱራሆማን ፥ የኢጣልያን ወዳጅነትና የበላይ ጠባቂነት ሁለቱም እንዲቀበሉ በመገፋፋት ያገሩንና የሕዝቡን ሁኔታ በቅርብ ሆኖ እንዲያጠናና ወታደርም እየመለመለ እንዲያዘጋጅ ከዚህ በፊት በአሳጊው ጦርነት ሰዓት ስሙን የጠቀስነው ይኸው ካፒታና ሳልቫቶሬ ፕርሲኮ በ1886 ዓ. ም. ወደ አውሳ መሐመድ አንፍሬ ዘንድ በነዋሪ ተቀማጭነት ተላከ ። ይኸው የኢጣልያ መኰንን የዐረብኛ ቋንቋና የእስልምናና ባህል ዐውቃለሁ ባይ ስለሆነ ፥ ለማሊያየቱ ተግባር ምርጫው እርሱ ላይ ወደቀ ።

ጄኔራል ባራቲዬሪ ፥ ይኸንን መኰንን በ1886 ዓ.ም. ወደ አውሳ ሲልከው በጽሑፍ ያሳሰበው ዋና ዋናው ከዚህ እንደሚከተለው ነው ።

የምሰጥህ ዝርዝር ትእዛዝ የለኝም ። እንዲያውም የሥራህን ነጻነት እንዳላጠብ ትእዛዝ ከመስጠት መራቅን እመርጣለሁ ። ነገር ግን የመልእክትህ ዋና ፍሬ ነገር የኢጣልያንን የበላይ ጠባቂነት የኤርትራን ቅኝ አገር ታላቅነት እየገለጽህ መሐመድ አንፈሬንና አውሳን ወደኛ ለመሳብና ለመያዝ ነው ። ይኸንንም ከዚህ ቀደም በጽሕፈትም ፥ በቃልም አዶራዎን እንደ ገለጽሁልህ በጥበብና በትዕግሥት የነሱን አሳብና ልማድ በመፈጸምና ከነርሱ ጋር በማናቸውም እየተመሳሰልህ ነው. . . ስለ ምኒልክ ሲነግ ደሀ ንጉሥ በኢጣልያ የበላይ ጠባቂነት ውስጥ መኖሩንና መልካም ግንኙነት ያለን መሆናችንን እንደሚረዳ ግለጽለት ።

መሐመድ አንፈሬ ፥ እጁ የሚል እንደሆነ የባንዳ ወታደር ለመመልመል አስብበት . . . በሐረር በኩል ሳያልፍ ያበሻ መንግሥት መገናኛውን በኛ በኩል እንዲያደርግ የአሰብ መንገድ በግድ የኛ መሆን አለበት . . . ከአዋሽ በላይ ያሉ የጋላ አገሮች ከወሎ ጋር የሚገናኙበትንና ለጦርነት የሚመቹውን ፍሬያማና ጠንካራ ቦታ መርምረህ እቅና ። ትራቬርሲ ዘውትር መልካም ነው እያለ ስለሚመካበት ስለ አዳል ጉቦ ስለ ጋሞቦ ትንሽ ነገር ማወቅ እፈልጋለሁ ። እንደዚሁም ፈረንሳዮች የሚያደርጉትን ለማወቅ ተጣጣር ።. . . ለዚህም ሁሉ ሥራህ አብዱራሆማን ይረዳሃል ። እርሱም ብልህ ነው ማናቸውንም ተስፋ የሚያደርገው ከኛ ነው ። ብዙ ነገር መጠየቅና ብዙ ነገር ያስፈልገኛል ማለት ይወዳል ። አንተም ይኸን ሲልህ ፥ መልእክቱ ሁሉ በመልካም ሲፈጸም ሁሉንም ታገኛለህ እያልህ የተለመደውን የብልሆት መልስ ስጠው ።

የሚወድህ ኦ. ባራቲዬሪ

ከረን 4/1894

እንደዚሁም ከካፒቴን ፕርሲኮ ጋር ቴኦንቴ ካርሎ ጂያኒኒ የሚባል ተላከና ሁለቱም አሰብ ከሚገኙ የኢጣልያ ኮሚሳሮች ከነፒስታሱዛ



እየተመካከሩ መሐመድ አንፋሬንና ልጆቹን እነመሐመድ አይዳሰን ፥ እንእንፈሬን ፥ መግሪያም ፥ ልዩ ልዩ ስጦታም እየሰጡ በልዩ ልዩ መንገድ የኢጣልያን ታላቅነት ፥ የኢትዮጵያን መንግሥት ታናሽነት ፤ ኢትዮጵያ በኢጣልያ ጥገኝነት ውስጥ መገኘቷን እያስረዱ ሁለቱን ዓመት ቆዩ ። በኋላም ካፒቴን ፕርሲኮ አምባላጌ መጥቶ ከሞተ ወዲህ አውሳ ያሉት ኢጣልያኖች የአምባ አላጌ ጦርነት የሆነ ጊዜ የተገላቢጦሽ ፥ "የምኒልክን ጦር የኢጣልያ ጦር አሸነፈው" ብለው አወሩ ። በአምባ አላጌ የኢጣልያኖችን ድል መሆንና የመቀሌን መከበብ ሁሉ እርግጠኛውን ነገር መሐመድ አንፋሬ እንዳያውቅ ፥ ከዐፄ ምኒልክ መልክተኛም ጋር እንዳይገናኝ ኢጣልያኖቹ እቀብቀው ሲጥሩ ቆዩ ። የዚህም ምክንያት እስካሁን ለመሐመድ አንፋሬና ለሌሎችም ሲሰብኩ የቆዩት የኢጣልያንን ኃያልነት ስለሆነ ፥ አሁን "የጋይለኛው የኢጣልያ ጦር በኢትዮጵያ ጦር ተሸነፈ" ማለት የተሰማ እንደሆነ የመሐመድ አንፋሬ አሳብ እንዳይለወጥና ከምኒልክ ጋር እንዳይደረብ ነው ።

መሐመድ አንፋሬ ፥ ዋናው ጦርነት እስኪጀመር ድረስ ከማዕከላዊው መንግሥት ከድቶ ጨርሶ ወደነርሱ መሆኑን ሳያረጋግጥ በጣም አወላውሎ ለሁለቱም ወገኖች ለየብቻ ታማኝነቱን ይገልጽ ነበር ። በመጨረሻ ግን ፥ ከኢጣልያኖች ወገን ተጽዕኖው ስለ በረከተበት ወደ ኢጣልያኖቹ ተደረበ ። አዳኙ ወልደ ጻድቅም የተለመደውን ያመቱን ግብር ቢጠይቁ ሳይልክ ቀረ ። ከአምባ አላጌ ጦርነት በኋላ ከዓድዋ ጦርነት በፊት ባለው ጊዜ ውስጥ ኢጣልያኖቹና ሽማግሌው መሐመድ አንፋሬ ፥ ልጆቹና ሹሞቹ በተተቀመጡበት ስብሰባ እየተደረገ ሲመከር ሲዘከር ሰንበተ ። በስብሰባውም ላይ አብዛኛውን ጊዜ ኢጣልያኖቹ ለመሐመድ አንፋሬ የሚወተውቱት ፥ "እኛ በሰሜን በኩል የምኒልክን ኃይል ጨርሶ ለማጥፋት የበቃ ኃይል አለን ። ነገር ግን ፥ እናንተም የኛ የቃል ኪዳን ጓደኛ እንደ መሆናችሁ መጠን ከድሉም በኋላ በግንባራችሁ ያለውን ለምለሙን አውራጃ ለመካፈል እንዲመቻችሁ አሁን በቶሎ ወደ እንኮበርና ወደ ሐረር የአውሳ ጦር ይላኩና ከሸዋ ጦር ጋር ይዋጋ ። በሸዋ ጦር ላይ የአውሳ ጦር የሚፈጽመውን አደጋ ሁሉ የኢጣልያ መንግሥት ከፍ አድርጎ እየገመተ ልዩ ልዩ ድጋፍና ገንዘብም መግሪያም ለመስጠት ተዘጋጅቷል" እያሉ ነው ።

ይኸ ሁሉ ሲሆን ፥ ከዐፄ ምኒልክ ወገን ከግብር ማስገበርና የፋቅ ግንኙነት ከማድረግ በቀር ኢጣልያኖች የሚያወሩትን እያስተባበለ ፥ በአምባ አላጌም በመቀሌም እየተሸነፉ መመለሳቸውን በተጨባጭ

የሚያስተነዝብ አልነበረም ። የሆነ ሆኖ ፡ አንፋሬ ግብር በመከልከሉ ዐጼ ምኒልክን መከዳቱ ታወቀ ። ኢጣልያኖችም ፤ "እርሱን መግረፍ አድርገው በእንኮበርና በሐረር ግንባር ጦር ሊልኩ ነው" የሚባል ወሬ ተሰምቶ ነበርና ዳግማዊ ምኒልክ ከአዲስ አበባ ተነሥተው ወሜሌ (ወሎ) በደረሱ ጊዜ ከዳቱን ስላረጋገጡ ፤ የሸፈተውን መሐመድ አንፋሬን እንዲወጉ ሦስት ታላላቅ መኳንንት ላኩ ። እነዚህም ራስ ወልደ ጊዮርጊስ አቦዬ ፥ ደጃች ተሰማ ናደው ፥ የእንኮበሩ አዛዥ ወልደ ጻድቅ ሲሆን የበላይ መሪውም አዛዥ ወልደ ጻድቅ ናቸው ። ምክን ያቱም ከሁለቱ መኳንንት በሥልጣን እንኳን ባይሆን በዕድሜ ስለሚ በልጡ ነው ። እንዲሁም ጦርነቱ የሚደረግበት የእንኮበርና የአውሳ አውራጃ የርሳቸው ክፍል በመሆኑ ጭምር ነው ። ሁለቱ ታላላቅ መኳንንት ራስ ወልደ ጊዮርጊስና ደጃች ተሰማ በሥልጣን እንዳይ ቀናቀኑ ተባብረው እንዲሠሩ ለማድረግ ከሁለት ላንዳቸው በመስጠት ፋንታ የጦር አበጋዝነቱን ለእንኮበሩ አስተዳዳሪ ለአዛዥ ወልደ ጻድቅ የሰጧቸውም ይመስላል ። የሆነ ሆኖ ፥ እነዚህ ሦስቱም መኳንንት የየራሳቸውን ጦር ይዘው በአዛዥ ወልደ ጻድቅ መሪነት በታ ኅሣሥ ወር በእርሳ ፥ በሁለዳዊ ፥ በሁምራ በኩል ሲያልፉ በጥር 17 ቀን ብዙ ጊዜ በማመንታት የቆየው መሐመድ አንፋሬ ጦሩን ይዞ መጥቶ ጦርነት ገጠማቸው ።

ስለ ጦርነቱ ግራዝማች የሴፍ ከተዉት ማስታወሻ በተጨማሪ በሌላ ጽሑፍ ሙሉው ባይገኝም ፥ እንዚሁ እንራስ ወልደ ጊዮርጊስ ወደ አውሳ ሲዘምቱ የዋሉበትንና ያደሩበትን መንገድ በዘረፉ ምክን ያት ከዳዊ አገር ባላገር ጋር ወታደር መታኮሱን ፥ በዚህም አዛዥ ወልደ ጻድቅ ፥ "ጠላታችን ገና ወደፊት እያለ በግና ፍየል ጥይቱን ከፈ ጀው እኔስ ለምን እሔዳለሁ ። ጠላታችንንስ በምን እንወጋዋለን"* ብለው ራስ ወልደ ጊዮርጊስንና ደጃች ተሰማን ተቆጡአቸው ።

ሁለቱም መኳንንት ወረራ የሔደውን ሰው ሁሉ ገርፈው ያመጣው ንም በግና ፍየል ደጀን ለቀለው ሰው እንደ ሰጡበት ይኸው ጽሑፍ ይገልጻል ። ከዚህ እያይዞ ኢቂ መስጊድ በስፈሩበት ጊዜ ፥ "እናንተ የመጣችሁት እኔን ለመውጋት አይደለም ፤ የምትሹት አብዱራሆማንን ስለሆን እሱ የሚገኘው ቴር ነውና ሚሌን ይዛችሁ ወደ ቴር ሒዱ ። ደግሞ እሽከሮቻችሁ አሽከሮቼን ገድለው ጦር ፥ ጋሻ ፥ ጨቤ ወስደዋ ልና መልሱ ። ከዚህም ስፍራ የዋላችሁና ያደራችሁ እንደሆን እዳል

* ትርጉሙ ወታደራችሁ በግና ፍየል እየቀማ ከባላገር በመታኮስ እዚሁ ጥይቱን በመፈጀት በኋላ ከመሐመድ አንፋሬ ጋር በምን እንዋጋለን ማለት ነው ።



መጀኑ ይፈጀችኋል ፤ ሚሌን ተሻገራችሁ እደሩ" የሚል የመሐመድ ሐንፈሊ (አንፋሬ) መልስ መጣ ። ከዚያ ከደባል ተነሥተው በጥር 17 ቀን ሰርዶ ሰፍረው ሳለ ፥ ከከተማው ጦሩን አስከትቶ የሁለት ቀን መን ገድ ተጉዞ መጥቶ ጦርነት እንደ ገጠማቸውና ድል እንደሆነ ፥ የመሐ መድ ሐንፈሉም አሊ የሚባል የሚወደው ልጅ ፥ የወንድሙ ልጆች ፥ ሦስት ያጐቱ ልጆች እንደሞቱ ይነበባል ። እንአዛዥ ወልደ ጻድቅም ከዚህ ድል በኋላ ወደፊት አልፈው ከከተማው አድሉ ገብ (ሐደሊ ገብ) በስፈሩ ጊዜ ፥ ኢጣልያኖቹ የሰጡት ወጨፎ ወተርሉ እንደ ተገኘ ፥ ከዚያ በኋላ ባገሩ ጠባቂ አድርገው እንደ ተመለሱ በማረጋገጥ የአ ውሳውን ታሪክ ይፈጽማል ።[1]

ሦስቱ ታላላቅ መኳንንት ፥ ኢጣልያኖች በጣም ተስፋ ያደረ ጉበትን ፥ መሐመድ አንፋሬን በጥር 17 ቀን ሲያሸንፉ ፥ ላገራቸውና ለንጉሣቸው ከፍ ያለ ሙያ ሠርተዋል ። በዓድዋ በኩል የተሰለፈው ዋናው ንጉሡ ያሉበት ጦር መኳንንቱም ፥ ወታደሩም ሞራሉ ከፍ እንዲልና ዋናውን ጦርነት በልበ ሙሉነት እንዲቀጥል አድርገው ታል ። የአውሳውን ድል ለመንገር ከነአዛዥ ወልደ ጻድቅ የተላኩት ሰዎች ዐጼ ምኒልክ ዘንድ የደረሱት በየካቲት 22 ቀን እንደሆነ ጸሐፈ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴ ገልጸውታል ።[2] በጥር 17 ቀን ድሉን ካገኙ ወዲህ ፥ መልእክተኞቹ ወደ ዐጼ ምኒልክ ለመድረስ ከአንድ ወር በላይ ጊዜ ፈጅተዋል ማለት ነው ። የዚህ ወሬ በትክክል በተሰማ በማግሥቱ የካቲት 23 ቀን የዓድዋው ጦርነት ተደረገ ማለት ነው ።

የእንኮበሩ ሊቀ አሊቃ ዘወልደ አዛዥ ወልደ ጻድቅ እዚህ (አውሳ) ድል አድራጊነት በቅድሚያ እንደቀናው አንተም ምኒልክ በዚያ (በዓ ድዋ) ደግመህ አሸንፍ ለማለት ቀጥሎ ያለውን ግሀልክ ቅኔ ተቀኙ ።

ምኒልክ ድግም ድሞፀ የብየ
እስመ ወልደ ጻድቅ ቀደመ ድሞፀ ይባቤ በገየ
ዓልየ ዘንግሠ ቅድመ ዚአከ
ወድኅረ ዚአከ ዘይነግሥ ዓልየ

1 ከፖሊስ ቤተ መዛግብት ከእጅ ጽሑፍ ክፍል የተገኘ ።
2 ታሪክ ዘመን ዘዳግማዊ ምኒልክ ... ገጽ 63



አጫኸር ወልደ ጻድቅ
ከዶ ካስትሮ ኔላ ቴራ ዴል ንጉሥ



ራስ ወልደጊዮርጊስ አቦዬ
ኢንአቢሲኒያ ከሚባለው ከእናራቶሪ መጽሐፍ

# ምዕራፍ ሠላሳ ስምንት

## በኢጣሊያኖች ዘንድ የጦርነት ምክር — በበላይ ተቃውሞ ከምሽግ ወጥተው ለመዋጋት እንደቆረጡ

ዐፄ ምኒልክ ዘንድ ባለፈው እንደ ተመለከትነው ፣ ጣልያኖች ከምሽግ ወጥተው አለመዋጋታቸው ፣ መረብን ተሻግሮ የመውረሩ ነገር በአንድ ወገን በወሃ እጦት የተነሣ መቅረቱ ፣ ወደሰሜን አቅጣጫ ጦር ሠራዊቱን እንዳያንቀሳቅሱ ጣልያኖችን ከምሽግ የማስወጣቱ አሳብ መሳቱ ፣ ስንቅ አልቆ ወታደር አንዳንድ ጊዜ እስከ ጄሬ ድረስ እየዘለቀ በዘረፋ ከባላገር ጋር መጣላቱ ከፍተኛ ችግር ፈጥሮ ነበር ። ይህ የተደራረበው ችግር ሁሉ አንድ መፍትሔ ለመፈለግ አስገድዷል ። ለዚህ ሁሉ የተገኘው መፍትሔ ፣ እንደ ምንም በሰላዮች አማካይነት አታሎ ከምሽግ ጣልያኖቹን እንዲወጡና እንዲዋጉ ማድረግ ስለሆነ ይህንኑ ለመፈጸም በየካቲት 23 ቀን በተደረገው የጦርነት ቀጠሮ ንጉሠ ነገሥቱና ራሶቻቸውም ትኩረት ሰጥተዋል ። በዚህም ተግባር የእንትጮው ተወላጅ ባሻ አውአሎም ከፍተኛ አገልግሎት አበርክተዋል ።

በዐፄ ምኒልክ በኩል ፣ ይኸን የመሰለ ችግር ሲኖር በጄኔራል ባራቲዬሪ በኩል ያለው ችግር ይነስ ይብዛ ተመሳሳይ ነው ። በሁለቱ ጦር መሪዎች መካከል ልዩነት ቢኖር ፣ እርሱ የበላይ አዛዦች ሲኖሩት ዐፄ ምኒልክ የበላይ የለባቸውም ። እርሱ ወደ ምሽጉ ለመሳብ ፣ እርሳቸው ወደ ሜዳ እንዲወጣ ለማድረግ በመምከር በዓላማ ይለያያሉ ። በሁለቱም የጦር ሠፈር የሁለቱም ወገን ሰላይ ተሠማርቶ ወሬውን ለየክፍሉ ያቀብላል ። በታማኝነት የሚያገለግሉትም እየተቀያየሩ ሥራቸውን በየበኩላቸው በትጋት ይሠራሉ ።

ጄኔራል ባራቲዬሪ ወጥቶ ለመዋጋት አዳጋች መሆኑንና ፣ በምሽግ መቆየቱም የስንቅ ማለቅ ችግር እንደሚያስከትል ተረድቶታል። በቅርብ ከድተው ወደ ወገናቸው የሔዱት እነራስ ሰብሐት የአጋሜንና የእንደርታን ሕዝብ ከማሳደም ጋር ከጀርባው መንገድ እያፈረሱና የስልክ ሽቦ እየቆራረጡ ፣ በማይ መሬት እንደሆነው ፣ አንድ አንድ ጊዜም ይዋጉታል ። ይኸ ሁሉ ተደራርቦ ሥጋትና አሳብ በራሱ ኃላፊነት ላይ ተንጠልጥሎ እንቅልፍ ነሥቶታል ።

ከሁሉ የበለጠ የሚያናድደው ከርሚ ጠቅላይ ሚኒስትሩ የሚያስተላልፍለት ምጸትና ወቀሳ አዘል ቴሌግራም ነው ። ባንድ ወገን ፣ "በአንድ ውጊያና ድል የአምባላጌንና የመቀሌን ውርደት ሊመልስ አልቻለም" ብለው በርሚ በርሱ እግር ፣ "ከርሱ በብዙ ረገድ የተሻለ ነው" ብለው የሚያምኑበትን ጄኔራል ባልዲሥራን እ.ኤ.አ. በየካቲት 22 ቀን ሾመውታል ።

በተወሳሰበ አሳብ ላይ የሚገኘው ጄኔራል ባራቲዬሪ ፣ "አበሾች አመሸግሁበት መጥተው ይወጉኝና እሸንፋቸዋለሁ" ብሎ ጠብቆ ሞኝ ባሊጋራ በግጣት ሳይሆንለት ከቀረ ወዲህ ፣ "ከአስንበት ከአዲግራት ወደኋላ ወደአዲ ኡግሪና ወደ ሰናፌ ተመልሰን ለስንቅ ማግኛው ለአሥመራና ለምጥዋ ቀረብ ባለው ሥፍራ ሆነን እንከላከል" አለ ። የበታች የጦር አለቆቹ ፣ "በአምባ አላጌና በመቀሌ ድል እየሆንን የለቀቅነው አገር አንሶ ፣ አሁን ደግሞ ከአዲግራትና ከሳውሪያ ወደኋላ ከተመለስን ጨርሶ የመሸነፍ ያህል ነው" ብለው ተከራከሩት ። በመጨረሻ የመጓጓዣና የስንቅ ኃላፊ ሌተና ኮሎኔል ራጋሞንቲ እ.ኤ.አ. ከመጋቢት 4 ቀን በኋላ ፣ በከብትና በስንቅ ማለቅ የተነሣ አዲግራትና ሳውሪያ ላለው ጦር ስንቅ ለማቀበል አለመቻሉን ለጄኔራል ባራቲዬሪ በቴሌግራም አስተላለፈለታል ። ስለዚህ የዚህ ሁሉ የችግር ሐተታ የተመኘነው ይኸው ጠቅላይ አዛዥ አንድ ውሳኔ በቶሎ ለመወሰን በግድ አስፈላጊነቱ ተሰማው ።

በዚህ ምክንያት ፣ ጄኔራል ባራቲዬሪ ወደኋላ ማፈግፈግ ወይም ወደ ፊት ገፍቶ መዋጋት የሚገባ መሆኑን ከበታች ጄኔራሎች ጋር ለመመካከር የካቲት 20 ቀን በድንኳኑ ውስጥ ሰበሰባቸው ።
የተሰበሰቡትም ፣

| | |
|---|---|
| ጄኔራል ጉሴፔ አሪሞንዲ | የብርጌድ አዛዥ |
| " አማኑኤል ዳቦርሚዳ | " " |
| " ማቴዎ አልቤርቶኔ | " " |
| " ጉሴፔ ኤሌና | " " |
| ኮሎኔል ቫሌንዛና | ሼፍዲታ ማዦር |

ናቸው ። እነዚህም በተሰበሰቡ ጊዜ ዋናው አዛዥ ሌተና ጄኔራል ባራቲዬሪ ከስንቁ ኃላፊ ከሌተና ኮሎኔል ራጋሞንቲ ፣ አሥመራ ከሚቀመጠው ከምክትሉ አገረ ገዥ ከጄኔራል ላምቤርቲ የተላኩትን ቴሌግራሞች ኮሎኔል ቫሌንዛናን እንዲያነብ አዘዘው ። ከተነበበና አንዳንድ ንግግር ከተደረገ በኋላ ጄኔራል ባራቲዬሪ እንደዚህ አላቸው ፣ "የመ



ጨረሻው ውሳኔ የሚሰጠው ከኔ በመሆኑ ፣ አሁን የጠራኋችሁ ስጦርነት ምክር አይደለም ። ነገር ግን እንደ ጸወትሩ ቅን ልባችሁን ገልጣችሁ አሳባችሁንና የጦር ሠራዊቱን ሁኔታ እንድትገልጹልኝ ነው ።"

ከዚህ በኋላ በመጀመሪያ ጄኔራል ዳቦርሚዳ እንደዚህ ሲል ተናገረ ።

> ስለውኑ ጊዜ አንድም ወታደር ከጠላት ጋር ከተሰለፍን ከሦስት ወር በኋላ ወደኋላ እንመለስ የሚል አይገኝም ፤ ኢጣልያም ወደኋላ ከመመለስ ሁለት ወይም ሦስት ሺህ ሰው በጦርነት መሞቱን ትመርጣለች ። እንዲያውም ስንቅ ከማለቁ የተነሣ ፣ ሌሎች እመርከብ ላይ ያሉት ወታደሮች ሳይደርሱ እኛው በቶሎ እንዋጋ . . . የወታደሩም ከፍ ያለው ሞራሉ (መንፈሱ) ወደኋላ እንመለስ ያልነው እንደሆነ ዝቅ ብሎ ይዋረዳል ። ሹማምንቱም ሁሉ አሳባቸው ከዚህ ያልወጣ መሆኑን በዋስትናዬ አረጋግጣለሁ ። ወደኋላ እንመለስ ያልን እንደሆነ ግን ፣ በቁጥር የሚበልጡን በጉዞና በመንገድ ከኛ የሚፈጥኑት መንገዱን ሁሉ የሚያውቁት ጠላቶችን ከሸፈቱብን ሰዎች ጋር ተሰግሥጎ በሰላዮቹ እየተመራ ተከታትሎ እየወጋ አደጋ ሊያደርግብን ይችላል ።[1]

ከጄኔራል ዳቦርሚዳ ቀጥሎ የተናገረው ጄኔራል አልቤርቶኒ ነው ። እርሱም ያገር ተወላጅ ጦር አዛዥ በመሆኑ ፣ ወዲያውም ያገር ውስጥና የኢትዮጵያንም ጦር ሁኔታ በስለላ የሚያስመረምር ነበርና በተራው እንደዚህ ብሎ ተናገረ ።

> የጠላት ጦር እየተጉደለ ሔዷል ። ግማሹ ወደ ሽሬ ለዘረፋ ተበትኗል ። ግማሹ ወደ ሸዋ መመለስ ጀምሯል ። ጎድጥ በቀረውም ጦር ላይ በሽታ ገብቶበታል ። . . . ጉብዙ ኮሎኔል ስቴቫኒ የሁለት ባታቶ . . . ካፒቴን አዴኔ የሁለት ክፍል (ኮምፓኝ) ጦር ይዘው ደርሰዋል ። ማዦር ባሉ ኃይለኛውን የገኛውን ባታቶ ጦር ይዞ ነገ ጧት ይደርሳል ። መድፎቻችን በደህና ሥፍራ ተመሽገዋል ። ወደ ጎድጥ የሚወስዱ መንገዶች ስለአሉ በነዚያ አልፈን ይኸን የሰነፈውን የጠላት ጦር አደጋ እንጣልበት ። እስካሁን ድረስ ባለው ጊዜ ስምምነት በመካከላችን ሳይኖር እዚህ ደርሰናል ። አሁን ግን ፣ ወደፊት አልፎ ለመዋጋት የሁላችን ፈቃድ ነው . . . ወደኋላ ያፈገፈግን እንደሆነ ግን ፣ እስካሁን ደክመን ያቋቋምነውን የጠላት ጦር ስቀን ቅኝ አገራችንን ለወረራ አሳልፈን መስጠታችን ነው ። ከዚህም በቀር ወደኋላ መመለስ የኛን ጦር መንፈስ ሃምሳ በመቶ ያቀዘቅዘዋል ።

ጄኔራል አልቤርቶኒ ፣ በስብሰባው ይኸን ቃል መናገሩን ጄኔራል ባራቲዬሪና ሌሎች ጸሐፊዎች ሁሉ በጻፉት ይገኛል ። ነገር ግን ፣ እርሱ ራሱ በኋለኛው ዘመን በጻፈው ማስታወሻ የቀረውን ሁሉ መናገሩን ሲያ

---

1 Adua, E. Bellavita, PP, 318 - 319 . La Prima Guerra d' Africa, R, Battaglia, PP, 733-786

ምን ፡ "ያበሸቓን መታመም ወይም ወደ ሸዋ መመለስ አልተናገርኩም" ሲል ክዷል ። ይኸውም የጦርነቱ የእጅግመሩ ምክንያት የስለላው ሥራ ስለነበረ ፡ አልቤርቶኒ ብዙ ጊዜ በምርኮ አዲስ አበባ ሰንብቶ ወደ አገሩ ሲመለስ የጦርነቱን ኃላፊነት ከራሱ ላይ ለማስወገድ "አላልሁም" ያለ ይመስላል እንጂ ፡ ከዓድዋ በፊት ባለው ጊዜ ሳይናገር አልቀረም ።

ከርሱ ቀጥሎ የተናገረው ጄኔራል አሪሞንዲ በፋንታው እንደዚህ አለ ።

> ያገርዋን ቋንቋ ሰላዮቹ የሚያመጡልን ከመጠን እያበዙ ነው ። ጠላት በመካከሉ ስምምነት ስለሌለው እኛን ለመውጋት ያመነታል ። ስለዚህ ከእንግዲህ ወዲያ ወደፊት ቀድሞ መውጋት እንጂ ፡ እዚህ ውጊያ መጠበቅ ከንቱ ነው ። እንደዚህ ከተሰበሰብን በአንድነት ወደ ፊት አልፈን መዋጋት ይቻላል ። ከውጊያም ይበልጥ በሽታ ሊጨርሰን ይችላል ። ወደኋላ መመለስ ወታደሮቻችንን አስገድ አልሆነ ሥፍራ ላይ ወደ መከላከል ያደርሰዋል ። ወደ ፈረሰው አገር ስንመለስ አገሬው ስለሚነሣብን ለጠላትም ይመቸዋል ። ከጠላት ጋር እንደዚህ ቅርብ ለቅርብ ተሰልፈን ብዙ ሳምንቶች ቆይተን ሳንዋጋ ማሳለፍም ስንፍና ነው ።

ከርሱ ቀጥሎ በመጨረሻ የተናገረው ፡ ባለፈው ጥር ወር ከኢጣሊያ አገር የመጣው ጄኔራል ጆሴፔ ኤሌና ነው ። ከሁሉ መጨረሻ የተናገረው በሽምግልናው መሆኑን ራሱ ከውጊያው በኋላ ጄኔራል ባራቲዬሪ በተከሰሰበት የወታደር ፍርድ ቤት ጉባዔ በሰጠው ምስክርነት ሲገልጽ ፡ ራሱ የተናገረው ቀጥሎ ያለው መሆኑን ጠቅሶ ያስረዳል ።

> አራተኛው ተናጋሪ እኔ ስለሆንኩ ፡ ሽምግልናዬ በመጨረሻ የመናገር መብት እንደሰጠኝ ገለጽሁ ። በተረፈ እጦሩ ግንባር (እምሽት) ከደረሰው 12 ቀኑ ብቻ ስለሆነ በጠላት ላይ ለቁጥሩም በመንገዱም በውጊያውም ስፍራ አመራረጥ በሁኔታው ሁሉ የግል አስተያየት ስለ ሌለኝ የምሰጠው ቃል መሠረቱ የጓደኞቼ አሳብ ብቻ ነው ። ስለዚህ የነርሱን አሳብ በመከተል ወደፊት ሔደን እንዋጋ የሚለውን ቃል ደግፌ የግል አሳቤን እንደዚህ በሚል ቃል ወሰንሁ ። "ወታደሮቻችንን አጠቃልለን እንሰብስብና ጠላታችንን ካለበት ድረስ ሔደን እንፈልገው ።"

ከመጨረሻው ተናጋሪ ከጄኔራል ኤሌና ቀጥሎ የተናገረውና ጉባዔውን የዘጋው ዋናው አዝማች ጄኔራል ባራቲዬሪ ነው ። በእውነቱ የርሱ አነጋገር አስተያየቱም ከነርሱ የተለየ ነው ። በሹመትም ከፍ ያለ በእእምሮም የበሰለ ስለሆነ ፡ እንደ ሌሎቹ የራሱን ጦር አጋና የኢትዮጵያን ጦር ሳያካክስ በአጭሩ እንደዚህ አለ ። "ምክሩ የድፍረት ነው ። ጠላታችን ጉብዝና ሞትን የሚንቅ ነው ። ለመሆኑ የወታደሮቻ



ችን ሞራል (መንፈስ) እንደ ምንድነው ?" ብሎ ጠየቀ ። ሁሉም ጄኔራሎች በተጠንቀቅ ቆመው "በጣም ጥሩ ነው" ብለው መለሱለት ። ከዚያ በኋላ ፡ "እጠላት ሰፈር ያሉት ሰላዮቻችን የሚያመጡልኝን እጠብቃለሁ ፤ እነርሱ ወዲያው እንደ ደረሱ አንድ ውሳኔ እቆርጣለሁ" ብሎ ጄኔራሎቹን አሰናበተ ። ዋንኞቹ የብሪጌድ ጦር አዛዦች ይኸን በሚመካከሩበት ጊዜ ፡ የቀሩት የጦር አለቆች ከድንኳኑ ውጭ ሆነው ውሳኔውን ይጠባበቁ ነበር ።[1]

በጄኔራል ባራቲዬሪ ንግግር በመጨረሻው ፡ "ከጠላት ሰፈር ያሉት ሰላዮቻችን የሚያመጡልኝን ከሰማሁ በኋላ አንድ ውሳኔ እቆርጣለሁ" ያለው የእንትጮው ተወላጅ ባሻ አውአሎም ነበር ። እርሳቸውም በስለላ እንደምን አገራቸውን እንዳገለገሉ ያገራችን ሽማግሌዎች ፡ ከሚያውቁት ጋር ካርሎ አናራቶሬ የሚባለው ኢጣልያዊ እንደዚህ ሲል ጽፏል ።

> ባሻ አውአሎም የሚባለው ከሰላዮቻችን አንዱ ነበረ ። እርሱም ለጠላታችንም ሰላይ ነው ። ከዓድዋ ጦርነት ከብዙ ቀን በፊት በራስ መንገሻ አቅራቢነት ከዐፄ ምኒልክ በተገናኘ ጊዜ የምሳ ብር ጉርሻ ተቀብሎ ራስ መንገሻ ሊያውቅ የሚፈልገውን እየመረመረ በመግለጽና እንደዚሁም ራስ መንገሻ የሚለውን ለባራቲዬሪ በመንገር ጠንከር እንዲሠራ ከምኒልክ እጅ ተቀብሎ ተሰናበተ ። ከዚህም ቀን በቀር ከንጉሡ ጋር ሁለተኛ አልተገናኘም ። ራስ መንገሻ እንደነገረው አውአሎም ወደ ጄኔራል ባራቲዬሪ መጥቶ ፡ "የኢትዮጵያ ጦር ስንቅ አልቆበታል ። ብዙም ወታደሮች ሞተዋል ፤ የቀሩትም ታመዋል ። ስለዚህ በዓድዋም ከመቆየት ወደኋላም ከመመለስ ፡ ወደፊት ወደ ቅኘው አገር መረብን ተሻግረው አልፈው ስንቅ ሊፈልጉ ነው ።" አለ ። ሆኖም ደግሞ በመጋቢት 1 ቀን 'የካቲት 23 ቀን' ንጉሡ እንደ ፊተኛው አሳቡ ወደኋላ ለመመለስ ነው ብሎ ተናገረ ። ከዚህም ወሬ የስንቁ ማለቅ የበሽታው መግባትና ወደኋላ ለመመለስ መታሰቡ እውነት ነው ። ወደፊት ወደ ኤርትራ ሊገቡ አስበዋል ያለው ግን አሉቱ ነው ። ባራቲዬሪ ለመዋጋት የቆረጠው በተለይ በነዚህ ወሬዎች ተመሥርቶ ይመስላል ።

ባሻ አውአሎም ፡ በ22 ሰዓት (ከሌሊቱ በ4 ሰዓት) የተደረገውን የኛን ስልፍ በተመለከተ ጊዜ የኢጣልያኖች ጦር መጣ ብሎ እንዲነግር አንድ ወጣት ላከ ። ምኒልክ ግን ፡ ሌሊት አገር ለመፈተሽ የወጡ ወታደሮች ይሆናሉ እንጂ ጣልያኖች ውጊያ ቆርጠው የሚወጡ አይመስለኝም ሲሉ መጠርጠራቸውን ገለጹ ። ቢሆንም በጥንቃቄ መጠባበቅ ነው የሚል ትእዛዝ ለራስ መንገሻ ላኩላቸው ። ይኸም ሰላይ ከጄኔራል ባራቲዬሪ ጋር ሆኖ ወደፊት ተጉዞ እኩለ ሌሊትም ራዓዮ ተራራ ሲደርስ ከኛ ጦር ውስጥ አምልጦ የቁራቁ ባታ ከመ

1 Memoire d' Afrique...(Chan.) XXX; Italia ed Etiopia, PP. 316-321

ጄኔራል ባራቲዬሪ ፣ በዚህ ዓይነት ሁኔታ ከፋፍሎ ከደለደለ በኋላ ፣ እ.ኤ.አ. የካቲት 29 ቀን (የካቲት 22 ቀን) ያወጣው ትእዛዝ የዳቦርሚዳ ፣ የአሪሞንዲና የአልቤርቶኒ ጦር እያንዳንዱ ከግታው በምሽት ሰዓት የሳውሪያን ምሽግ እየለቀቀ በዓድዋ አቅጣጫ ጉዞውን እንዲጀምርና እነርሱም ጉዞ ከጀመሩ አንድ ሰዓት ቆይቶ ተጠባባቂው የኤሌና ጦር ተከትሎ እንዲጓዝ ነው ። አስቀድሞ እንነጋገር ሳልሳ ያዘጋጀት ያገር ፣ የስፍራ ፣ የወንዛ ወንዝና ፣ የተራራዎች ምልክት ያለበት የጦር ፕላን ተሠርቶ ስለነበረ ፣ የዚሁ ፕላን እንዳንድ ግልባጭ ለአዝማቾች ተሰጥተአቸዋል ። ሊዋጉ ያሰቡት በደንበኛ ፕላን ስለሆነ ፣ በዚህ በፕላኑና በምክርም በተወሰነው መሠረት የቀኙ አዝማች የዳህላን በር የረቢ አሪዮኒን መንገድ ይዞ እንዲጓዝ ፣ የመካከለኛው አዝማችና ተጠባባቂው ጦር የእንዳ ጉብጣን አቅጣጫ ይዞ እንዲጓዝና የግራው አዝማች በኪዳነ ምሕረት በር በኩል እንዲሔድ ተወስኗል ።

እንደ ወጣው ትእዛዝ ፣ እያንዳንዱ ወታደር 112 ጥይት ፣ የሁለት ቀን ስንቅ ፣ ከላይ የሚደርበውን ካፓ (መንጠልያ) ፣ የወሃ ኮዳና የዳቦ መያዣውን እንዲይዝ ፤ የእርድ ከብት ከነመጋሪያው በሠራዊቱ ኋላ እንዲጓዝ ፤ የገኒ ክፍሎች (ምሽግና የጦር ስፍራ የሚያከናውኑት) ስልከኞችና ቴሌግራፍ አስተላላፊዎች መሣሪያዎቻቸውን ይዘው በየክፍላቸው ሆነው ከየክፍሉ የጦር አለቆች የሚሰጣቸውን ቃል ለመቅዳፉ ሹም በፍጥነት እንዲያስተላልፉ ትእዛዝ በዝርዝር ተሰጥቷል ። ምንም እንኳን ጦሩ በቀኝ ፣ በግራ ፣ በመካከልና በኋላ አራት ላይ ቢከፈል ፣ ከዋናው ሰፈር ለጦርነት ጉዞ የሚጀመርበት ሰዓት ቢለያይ ፣ አንዱ ሠራዊት ሌላውን ርቆት እንዳይሔድና ተነጥሎ በመንገድ ከጠላት ጦር ጋር ብቻውን ገጥሞ አደጋ እንዳይደርስበት ከበላዩ አዛዥ ለየጄኔራሎቹ ጥብቅ ትእዛዝ ተሰጥቷል ። የመንገድ መሳሳትም እንዳይኖር ተጠንቶ የተዘጋጀው የካርታ ፕላን ለየአለቆቹ ከመታደሉ በቀር ፣ በአገሩ ውስጥ ሆነው የሚያገለግሉት ያገር ተወላጆችና ባላገሮች መንገድ እንዲመሩ እየተከፋፈሉ ለየክፍሉ ጦር ተሰጥተው ነበር ።

ከነዚህም ጋር የዓድዋን አካባቢ የሚያውቅ እንደሚረዳው ፣ ሜዳ ቢኖርም በሜዳው ላይ ተበታትነው የሚታዩ ብዙ ጉብታዎች ስላሉ ፣ በነዚህ ጉብታዎች ሆነው "ቴሌግራፍ ኦፕቲክ" በሚባል መሣሪያ እየተመለከቱ ፣ "ስንቱ ረዳት ጦር ይጨመርለት ፤ እነሱ ወደፊት ይግፉ ወይም ወደኋላ አፈግፍጎ ለእነሱ ይደረብና ይኼን ስፍራ ይያዝ" የሚል ትእዛዝ የሚሰጡ የፕላንና የሎጂስቲክ ሹማምንት ተመድበዋል ። የነርሱን ትእዛዝ ደግሞ እያቀጠኑ ለየክፍሉ የጦር አለቃ የሚያደርሱ የፈረሰኛ ጓዶች አሉ ። ተዋጊ የጦር አባል ሞቶ ወይም ቆስሎ በወደቀ



ጊዜ በቶሎ እንዲሞተው የሕክምና እርዳታ የሚያደርጉት ሁሉ በየክፍላቸው በደንብ ተደልድለው ተሰልፈው ነበር ።

እንደዚሁም ፣ ወሬው ለኢትዮጵያ ጦር ደርሶ ተጠንቅቀው እንዳይጠብቁ በማለት ከሰፈር የሚነሣው ጊዜና ሰዓት ለማንም እንዳይነገር በጥብቅ ታዞ ነበር ። ነገር ግን ይኼ ሁሉ ከኢትዮጵያ ባለሥልጣኖች ጋር ያመለጠ አልነበረም ። ጦርነቱ ካለቀ በኋላ ግራዝማች የሴፍ ተማርኮ በኢትዮጵያውያን እጅ ከገባው ከጄኔራል አልቤርቶኒ ጋር ጭውውት ሲያደርጉ ፣ ስለ ስለላ ጉዳይ እንዲሞተው በተነጋገሩበት ጊዜ ፣ "እናንተ ሰላዮቻችን የምትሏቸው ምኒልክ የላኳቸውን ነው ። የናንተ ሰላዮች ይነስ ይብዛ በሙሉ ለንጉሡ የሚታዘዙ ናቸው ። እርግጠኛውን በናንተ በኩል የተደረገውን በትክክል ይነግሩን ነበር" ብለው እንደጫወቱትና የተማረኩትም የኢጣልያ ሹማምንቶች ከባታተ ወታደሮቻቸው ውስጥ ሰላዮች የነበሩትን እንደ ተመለከቷቸው ፣ አልቤርቶኒ ወደ አገሩ ከተመለሰ በኋላ ያወጣው ማስታወሻ በኮንቴ ሮሲኒ ታሪካዊ መጽሐፍ ላይ ተብራርቶ ተገልጿል ።[1]

እዚህ ላይ አንባቢ ሊገነዘበው የሚገባው ፣ በዚህ ጊዜ በኢትዮጵያ በኩል የነበረውን የተሳካ የጦር ድርጅት ብቻ ሳይሆን ለድል ዋና መድን የሆነውን የስለላ ሥራ ነው ። የጦርነቱንም ድል ያስገኘው ምንም እንኳን የሠራዊቱ ዠግንነት ፣ የንጉሠየው ፣ የነታፈሰና የነበሻህ አቦዬ የጋለ አርበኝነት ቢሆንም ፣ ለመዋጋት ዕድል የተገኘው ከምሽግ አልወጣም ብሎ ያስቸገረው የኢጣልያ ጦር በነዚሁ ሰላዮች ተታሎ በመውጣቱ ነው ። የኢጣልያን ጦር ያወጣውን ሁኔታ ፣ የጉዞውን ፣ የጦርነቱን አጀማመርና ፍጻሜ በሚቀጥሉት ምዕራፎች እንመለከት ።

1 Italia ed Etiopia.. PP. 325 - 326.

# ምዕራፍ ሠላሳ ዘጠኝ

## የዋናው ጦርነት አጀማመርና ፍጻሜ በጸሐፌ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴ ጽሑፍ

የኢጣልያ ጦር ፣ በ1887 ዓ.ም. በኮአቲትና በሰንዓፌ ራስ መንገሻን፣ ደብረ ኃይላ ላይ እንቀኛዝማች ኃይለ ማርያምን በጦርነት ያሸነፈ ጊዜ "ከዚህ በኋላ የኢጣልያንን ጦር ማንም ሊመልሰው አይችልም ፤ የሚቋቋመን ቢኖር ፣ ሁልጊዜ አሸናፊዎቹ እኛ ነን" የሚል ጽኑ የተዋሀደት እምነት ሮማም ለቅኝ ግዛት በመጡትም ኢጣልያኖች ዘንድ አደረ ።

በዚህ ምክንያት ፣ ከደብረ ኃይላ ጦርነት ወዲህ ልጓሙ እንደ ወለቀለት ፈረስ ከደብረ ኃይላ እየፎለለ ረግዥሙን የኢጋሜን ፣ የአንደርታን ፣ የእንዳ መሆኒን ወረዳዎች አልፈው ቀጀራት ፣ እሸንጌ ሐይቅ አጠገብ ደረሱ ። በንጉሡ ነገሥቱ ከኋላ የተደገፈው ግንባር ቀደሙ የንጉሥ መኰንን ጦር መጠጋቱን ሲሰሙ ፣ ከእሸንጌ ሐይቅ ወደኋላ መለስ ብለው አላጌ ላይ መሸጉ ። የአላጌው ጦር ሲፈርስ እንደ ታላቅ ውርደት ቆጠሩት ። በቁጭት " የአላጌውን መሸነፍ እንመልሳለን" ሲሉ የመቀሌው ተደገመ ። "ሁለቱንም ውርደቶች በእጥፍ እንደማያዳግም አድርገን እንመልሳለን" ሲሉ የዓድዋው ተመለሰ ። ጣልያኖቹም ወደፊት እንደምናነበው ፣ "በዓድዋ ድል ሳናደርግ መታረቁ የኢጣልያን ክብር ይነካል "ብለው በሮማ ዋና ምክር ቤት ተከራከረዋል ። ሦስተኛውም ውጤቱ የመሸነፍ በትርና ውርደት ማግኘት ሆነ ። ከዚህ ሁሉ ሽንፈት በኋላ ፣ በየጊዜው ተለምነው የገፈተሩትን ዕርቅ ሁሉ በመጨረሻ በግዳጅ ሊቀበሉ ተገደዋል ።

በዚህ ዘመን ፣ በኢትዮጵያ በኩል የታየው የጦር አመራርና የፖለቲካው አረማመድ ዘዴ አስደናቂ ነው ። ደንበኛ የጦርና የፖለቲካ ትምህርት ያልተማረው ወገን ፣ ተማርኩና ሠለጠንኩ የሚለውን ወገን በሁለቱም ግንባር አሸንፎታል ። ኢትዮጵያውያን በዝግታ ፣ በትዕግሥት ዕለት በዕለት የጦር ኃይላቸውን እያጠናከሩ ሲሔዱ ባገኙትም ድል ኩራትና ትምክህት አሸንፏቸው ሳይገነፍሉ ፣ በየድሉ ማግሥት የሰላም እጃቸውን ለኢጣልያ ሲዘረጉ ቆይተዋል ። የሁለቱን ጦር ሠራዊት ዕድል የወሰነው የዓድዋው ጦርነት ተጀምሮ ሳለ ፣ ጣሊያኖች የተማመኑበት ግንባር

ሳገራቸውና ለሃይማኖታቸው ደንባቸው የሚፈትድላቸውን የእምነትንና የመንፈሳዊ እባትነት ሥራቸውን መፈጸማቸውን ያመለክታል ። በጊዜው የነበረው መንግሥትና ሕዝብ ኅብረት አንድ በመሆን ፣ በወራሪነት የመጣበትን ዘመናዊ መሣሪያ የታጠቀውን ጠላት ከቶም መትቶ እሸንፈው ። ይህም በአፍሪካ አህጉር ከዚህ በፊት ያልተደረገ ድል አድራጊነትን የሚያንጸባርቅ የድል ኮከብ ብርሃን በኢትዮጵያ የነጻነት አየር ላይ እንደ ፈነጠቀ ኖረ ።

ከሁሉ በበለጠ ሁኔታ በውጫሌ የውል ክርክር ጊዜ ፣ በፖለቲካው ተግባር ያልተለዩትና በእንቶኔሊና በኢጣልያኖች የወራሪነት ሐሳብ ሲናደዱ ሲቆጩ የቆዩት እቴጌ ጣይቱ ፣ በዚህ በዓድዋ ጦርነት የሠሩትን መያ ጽሑፉ እንደልቶ የተናገረውን ተመልክተናል ። ድል ማድረግም ፣ ድል መሆንም የሚመነጨው ከእግዚአብሔር ፈቃድ መሆኑን በመገንዘብ በትድግሥ ጦርነቱ ሲጀመር ፣ በማኸራታቸው ድንጋይ ተሸክመው ፣ በጉልበታቸው ተንበርክከው እግዚአብሔርን በጸሎት ከለመኑ በኋላ ፣ ቀጥሎ ጦርነቱ ተጀምሮ እስኪጨረስ ድረስ ከንጉሡ ነጋሪት ኋላ ከዳዳሉ ጉን ሆነው ለተጠማ መጠጥና ውሃ እየሰጡ ፣ የቆሰለውን እያሳከሙ ፣ የሚሸሽ ወይም ወደፊት ለመግፋት የሚያመነታውን ሲያገኙ ለእቴጌነታቸውና ለቁንጅናቸው መሸፈኛ የሆነውን ዐይነ ርግብ ከፊታቸው ላይ እንሥተው እንደ ወንድ ፣ "ወደፊት ግፋ በለው" እያሉ በጩኸት እየተናገሩ ሲያዋጉ መዋላቸው ፣ ይልቁንም አንዳንድ ወታደር ወይም የጦር አለቃ ተዋግቶ ለጊዜው የማረከውን የጣልያን ወታደር ወደኋላ እርሳቸው ወዳሉበት ይዞ ሲመለስ ፣ "ንጉሡ ሳይመለሱ የት ነው የምትመለሱት ፣ አሁንም ምርኮኞቻችሁን ለኔ አስረክቡኝና እናንተ ተመልሳችሁ ውጊያውን ቀጥሉ" ያሉት ፣ ለዚህ ጦርነት ከንጉሡ ነጋሪት ቀጥለው ደንበኛ አሳቢ ትጉኅ መሪና አዋጊ መሆናቸውን እንገነዘባለን ። የጦርነቱ ድል የሚገኘው ጠንክሮ በመዋጋት እንጂ ፣ ጣልያንን ማርኮ በመመለስ አለመሆኑን ተገንዝበው ምርኮኛህን ለኔ ተወው ፣ ጦርነቱን ቀጥል ማለታቸው በአስተዋይነት መምራታቸውን ያስረዳል ። እንደዚሁ አድርገው ጠቅላላው ጦር የሚዋጋበትን ሲያስቡ ፣ በተለይ የግላቸው ቁጥሩ ከአምስት እስከ ስድስት ሺ የሚደርሰው ጦራቸው በውስጡ አራት መድፍ ይዞ መዋጋቱም አይዘነጋም ።

በጸሐፊ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴ ጽሑፍ ላይ ፣ "የኋለኛው ሰልፍ እንደ መወዘወዝ (ይኸውም ማለት እንደ ማወላወል) ሲል ባዩት ጊዜ ፣ እቴጌ ቃልምን እፈፍ አድርገው (ይኸውም ማለት ጮኸው) ተናገሩ ። "እደምሀ አንተ ምን ሆነሃል ድሉ የኛ ነው ብለው አሉት ። ሰዉም የተናገሩትን ቃልና እቴጌን ባየ ጊዜ ሴት ሲያጣና (ሲያበረታ) ወንድ መሸሽ አይሆንለትምና ጸና አለ" ወደፊት በሚነበበው በኢጣልያንኛው ጽሑፍ ላይ ደግሞ ፣ "በዚሁ ጊዜ ተጠባባቂው የ7ኛው ቢታሊዮን ጦር ደርሶ አንድነት ያደረጉት መቋቋም ሐበሾችን ወደኋላ 1000 ሜትር ያህል እንዲያፈገፍጉ አደረጋቸው" የሚለው ተገናኝቢ ነው ። ዐይን ርግባቸውን ገልጠው ወይዘሮ ዘውዲቱንና ደንገጡሮቻቸውን አስከትለው በኢጣልያኖች መቋቋም የተነካ የኛን ወታደር ማፈግፈግ ሲያዩ ፣ "ምን ሆንክ አንተ ድሉ የኛ ነው ብለው" ያሉት በዚህ ጊዜ ነው ማለት ነው ። ይህ አንድ መስመር የማይሞላው ኃይለ ቃል እኅታቸው ወይዘሮ አፃለች ወደኋላ በምርኮ ሰበብ ሊመለስ ሳሰበው ጦረኛ ወታደር ፣ "ንጉሥህን ትተህ የምትመለሰው ዓድዋ ቤት አለህን" ብለው ከሠነዘሩት ጋር ተባብሮ ታላቅ የድል ፍሬ ካስገኙት ሰበቦች አንዱ ነው ማለት ይቻላል ።

ስለዚህ ፣ በዚህ ጦርነት ከጦር ሠራዊቱ እኩል በየተግባራቸው ተሠማርተው ዘመቻውን የተካፈሉትን የቤት ክህነት ሰዎች ከአቡነ ማቴዎስ ጋር ፣ ሴቶቹንም ከእቴጌ ጣይቱ ብርሃን ዘኢትዮጵያ ጋር በዚያን ጊዜ ባሳዩት መሥዋዕትነት በተገኘው ድል የተጠቀምንና ዛሬ የምንመካ ኢትዮጵያውያንና ኢትዮጵያውያት ሁሉ ሳናደንቅና ሳናመሰግን አናልፍም ። እንግዲህ በኛ በኩል የጦርነቱን አገማመሩን ፣ አካሔዱንና አፈጻጸሙን ከጸሐፊ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴ መጽሐፍ ላይ በዚህ ዓይነት ከተገነዘብን በኋላ ፣ በኢጣልያኖቹ በኩል የካቲት 22 ቀን በዋናው ጦርነት ዋዜማ ሲመከርና ሲዘከር ተውሎ ለ23 አጥቢያ ሌሊቱን ተጉዘው ጦርነቱን የጀመሩበትን ሁኔታ በሚቀጥለው ምዕራፍ እንመለከታለን ።

በዚህ ታላቅ ጦርነት ሽማግሌው ራስ ወልደ ሚካኤል ሰሎሞን የንጉሥ ኃይለ መለኮት አባት ምንም በእድሜ ገፍተው ቢያረጁ የአሽከራቸውን እጅ እንደጨበጡ ይዋጉ ነበር ። እንደርሳቸውም በእድሜ የገፉት በዠግንነት የታወቁት ራስ ደረሶ ምንም እንኳን የጦር አዛዥነቱ ወደ ራስ መርዕድ ቢዛወር ከንጉሥ ተክለ ሃይማኖት አልለይም ብለው መጥተው ጦርነቱን ተካፍለዋል ። ይኸ ሁሉ ያገር አፍቃሪነትንና አንድነትን ያመለክታል ።



ጸሐፌ ትእዛዝ ገብረሥላሴ
ከሞሪስ ደኮፔ



ከዓፄ ምኒልክና ከእቴጌ ጣይቱ ጋር በኅብረት የዓድዋን ጦርነት
የተካፈሉት ጳጳሱ አቡነ ማቴዎስ
ከሞሪስ ደኮፔ

# ምዕራፍ ዐርባ

## የኢጣሊያኖች የሌሊት ጉዞ — የግራው አዝማች ጦር መደምሰሱ— የአርበኛው ጦር አበጋዝ የፊታውራሪ ገበየሁ አሟሟት — የጄኔራል አልበርቶኒ መማረክ

ማናቸውም ድርጅትና ዝግጅቱ ከተደረገ በኋላ፣ የካቲት 22 ቀን ከማታው በሦስት ሰዓት ከራብ የጄኔራል አልበርቶኒ፣ የጄኔራል አሪሞንዲ፣ የጄኔራል ዳቦርሚዳ ጦር ተሰልፎ ከምሽጉ ወጣ። በአራት ሰዓት ተኩል ላይ ተጠባባቂው የጄኔራል ኤሌና ጦር ተከተለ። ዋናው አዝማች ከደጀን ጦር ፊት ታጅቦ ይጓዝ ነበር። ከሰፈራቸው ዓድዋ ኢትዮጵያውያን እስካሉበት ድረስ ርዝመቱ 15 ኪሎ ሜትር ስለሆነ፣ ይህ ጉዞ 8 ሰዓት እንደሚፈጅባቸው ገምተው እንደነበረ ባራቲዬሪ ያረጋግጣል። የጦር መኰንኖቹ ጦርነት እያማራቸው አለቃቸው ጄኔራል ባራቲዬሪ በኃላፊነቱ ምክንያት ለዝግጅቱ ሲል የጦርነቱ ጊዜ ወደ ኋላ በመራዘሙ፣ ከማማረር ሌላ በቀር ጄኔራሎቹም ወታደሮቹም በተለይም በቅርብ ጊዜ ከኢጣሊያ አገር የመጡት ሹማምንቶችና ወታደሮች እየተበሳጩ በጄኔራል ባራቲዬሪ ላይ ሲያጉረመርሙበት ነበርና አሁን የናፈቁትን ጦርነት ለመግጠም ጉዞው በመጀመሩ ሁሉም በልቡ ደስታ እየተሰማው አስቸጋሪውን የሌሊት መንገድ መጓዝ ጀመረ። ምንም መንገዱ ወጣ ገባ፣ በቀላ ሜዳ ለተሸፈኑ ለፈረንጅ እግር የማይስማማ ቢሆንም፣ ይህ ሌሊት ሙሉ የጨረቃ ሌሊት ስለነበረ የደስታ መንገዳቸውን ይበልጥ አቃናላቸው።

ከሦስቱ ዋና አዝማቾች አንዱ የግራው አዝማች ጄኔራል አልበርቶኒ የሦስቱ ጦር ሠራዊት ሳይለያይ እየተጠባበቀ በአቅራቢያ ሆኖ እንዲጓዝ ተብሎ ከበላዩ ከጄኔራል ባራቲዬሪ ከፕላን ጋር በጽሑፍ የተሰጠውን ትእዛዝ ተላልፎ ወደፊት ገሥግሦ በመጀመሪያ ጦርነት የጀመረ እርሱ ነው። ይኸንን ያደረገበትን ምክንያት፣ ብዙ ጸሐፊዎች በልዩ ልዩ ዓይነት ተርጕመውታል። ግማሾቹ "የአበሾቹን ኃይል በመናቅ ብቻዬን አሸንፋቸዋለሁ ብሎ ነው" ሲሉ፣ ግማሾቹ "በአለቃው በባራቲዬሪ ላይ እርሱና አሪሞንዲ ንቀት ስለ ነበራቸው፣ እርሱ ቀድሞ ብሎ ከአበሾቹ ጋር ተዋግቶ የድል አድራጊነትን ዝና ለማሉ

ውስጥ እየገባ ተሰማ ፡ ወዲያው ተመልሰው የኢጣልያኖችን መምጣት ተናገሩ ። በዚህም ጊዜ ምኒልክ የድንጋጤም ፡ የመበርገግም መልክ አልታየባቸውም ይባላል ። በእቴጌ ቆመው ጥቂት ደቂቃዎች እንደቆዩ ወደ አቡነ ማቴዎስ ጠጋ ብለው ትንሽ ንግግር ከተለዋወጡ በኋላ ተመልሰው አስተራቸው ቆሙ ። ከዚህ በኋላ አቡነ ማቴዎስ በቀኝ እጃቸው መስቀላቸውን ከፍ አድርገው ይዘው በዚያ ላሉት ሁሉ እንደዚህ ብለው አስተዋዝነው ለትስ ጭምር ተናገሩ ። "ልጆቼ ሆይ ዛሬ የእግዚአብሔር ፍርድ የሚፈጸምበት ቀን ነው ሒዱ ለሃይማኖታችሁና ለንጉሣችሁ ሙቱ ኃጢአታችሁም ይሰረይላችኋል (እግዚአብሔር ይፍታ)"

አቡኑ ይኸን ተናግረው ሲጨርሱ ፣ መኳንንቱ ሁሉ እየተሽቀዳደሙ የአቡኑን መስቀል ተሳልመው ከሄዱ በኋላ ፣ እያንዳንዱ በየክፍሉ ወደየስፍራ ሒዶ በስፍራም የነበረው የውጊያውን መጀመር ሰምቶ እመጃጋጀቱ ላይ ነበር ። ንጉሥ ተከለ የይማኖት ብቻ ቁርባን ለመቀበል ሊቆዩ አስበው ነበር ። ነገር ግን ፣ ዐፄ ምኒልክ ኃጢአትም ወርደል ፤ ይልቅስ እዚህ መቆየት አያጋ ነው ስለአሏቸው እርሳቸውም ወጥተው ሔዱ ። በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ምኒልክ ብቻ ቀሩ ።

ማጆር ቱሪቶ የያዘው የኪዳነ ምሕረት በር ጎድጉ ስለፈረው ለዋናው ለጀኔ ጦር ወሰለ ብሎ ይታየው ነበር ። ... የኢጣልያን ጦር መምጣቱን ሲያረጋግጡ የንጉሥና የራስ ሚካኤል ጦር ደግሞ ፡ በግራ በኩል ለመከበብ ወደ ኪዳነ ምሕረትና ወደ እባ ገሪማ ጉብታ ተጓዘ ። ደጃች በሻህም ፈረሰኞቻቸውን ይዘው በጉን ሜዳ ቆደሙ ። አጋማሽ የራስ መንገሻ ጦር በቀኝ በኩል ወደ ማይ አጋም ዘለቀው በገርባ ሊመጡ ነበር ። ነገር ግን በባን ቀይዕ ሲደርሱ በዘዶ ቀርቶ ወደ ጎድጓ ወደ ማርያም ሸዊቶ የሚያሳልፈውን የረቢ አሪቀኒን መንገድ ... እንዲይዙ ታዘዙ ። የንጉሥም ጦር ከጎደጓ መጥቶ የበባን ቀይዕን ስፍራ ይዞ ከቆየ በኋላ ፣ ማይ አጋም ወጥቶ ከአልቤርቶኒ ጦር ጋር በማርያም ሸዊቶ ከጀኔራል ዳቦርሚዳ ጦር ጋር ውጊያው ተጀመረ ።

በዚህ ጊዜ ፣ ጀኔራል አልቤርቶኒ ያለበትን ሁኔታ ለማስታወቅ ለጀኔራል ባራቲዬሪ እንደዚህ ሲል 6፡30 (በ12 ሰዓት ተኩል) ላይ ጻፈ ። "ጠላት ሳያውቅ የኪዳነ ምሕረት በር በ11 ሰዓት ተያዘ ። ጠላት በጎድጓ ዙሪያና በማርያም ሸዊቶ ይገኛል ። የአንደኛው ባታሊዮን ጦር (ቱሪቶ) ከበሩ አልፎ ወደፊት ዘልቆ የተቀላቀለ ጦርነት እግድረግ ላይ ነው ። እርሱንም በመርዳት ባንዶች እብረው ይዋጋሉ ። ሁለተኛው ባታ በቀኝ ያለውን ተራራ ይዟል ። የቀሩት ሁለት የባታ ወታደሮች መድፋቸውን እንደያዙ ተሰብስበው ይጠባበቃሉ ። ትልቅ ጦርነት ሊደረግ የተቃረበ መሆኑ የተረጋገጠ እንደሆነ ይሰማኛልና የእሪምንዳ ጦር ተቀላቅሎ ይድረስ ። ግግኙነትም የጠላት ጦር እንዲይዝልን የዳቦርሚዳ ጦርም ወደፊት ቢገሠግሥ መልካም ነው ።" "ጀኔራል አልቤርቶኒ መልክቱ በ7፡30 (በአንድ ሰዓት ተኩል)እንደሚደርስ አስቦ ነበር ። ነገር ግን ለባራቲዬሪ የደረሰው ከ8፡30 (ከሁለት ሰዓት ተኩል) በኋላ ነው ።

ግንባር ቀደም ሆኖ ጦርነቱን የጀመረው የማጆር ቱሪቶ ጦር ፣ በጥይትና በመድፍ አንዳንድ ጊዜ በሳንጃ የጨበጣ ውጊያ አድርጎ



ሐበሾቹ ስለአዩት ፣ ጥግ እየያዙ የቀረው ሊማርክ ሊቀብል ። ከዚያ የተረፈው በዚሁ በቁራት እየተመራ ወደኋላው ሸሽቶ ወደ ዋናው ወደ አልቤርቶኒ የጦር ሰፈር ደረሰ ። ... የሐበሾቹም ጦር እየተከታተለ ደርሶ ዋናው ጦርነት ስለ ተጀመረ ፣ ጀኔራል አልቤርቶኒ የቀረው በመድፍና በጠመንጃ በሚዋጋበት ጊዜ ቫርጋል የሚባለው የሚፈነዳ ቦምብ እንዲተኮስ አዘዘ ። ይኸንንም ማድረጉ ሐበሾቹ በዚህ ተሸፍነው ድንጋጤ እንዲሸበሩ ነው ። በዚሁ ጊዜ ሐበሾቹ 1500 ሜትር ከፊ የሚሆን ቅርበት ያለውን ስፍራ ይዘው አንድ አንድ ጊዜ 1000 ሜትር ተጠግተው ሲዋጉ በዚሁ ቦምብና በመድፍ ብዙ ሰው አለቀባቸው ። ወደኋላም ማፈግፈግ ሲጀምሩ ፣ ጀኔራል ባራቲዬሪ ለአልቤርቶኒ የላከው መልስ መጣለት ። ደብዳቤውም የሚገልጸው የአሪሞንዲ ጦር ... በረቢ አሪቀኒ ተጠግቶ ጦር በገንደብታ መንገድን ነው ... በዚህ መካከል የአባ ገበር የሰበረው ፊታውራሪ ገበየሁ ጦሩን ይዞ ለወታደሮቹ ምሳሌ በመሆን እፊት ሆኖ እየመራ በግራ-ጋሚ ወደ ጦርነቱ ገባ ። ከርሱም ጋር ሦስት ወይም አራት ሺ የራስ ሚካኤል ፣ ሦስት ሺ የፊታውራሪ ተክለ አንድ ሺ አምስት መቶ የፊታውራሪ ተፈሪ ጦር ደረሰ ። ከዚህ በኋላ በሁለቱ መካከል የሚደረገው ጦርነት ከእክ ያለፈ የጋለ ሆነ ። ከሁለቱም ወገን በኋላ የነበሩት እፊት ሆነው ለጀመሩት እየደረሱላቸው የብዙት ውጊያ ሲደረግ የጥይቱ ጩኸት እስደናቂ ነበር ። ... ከኢጣልያኖቹ ወገን እያንዳንዱ ወታደር 142 ጥይት ብቻ ይዞ ነበርና* ። ጥይት በማለቁ የመሸነፍ አደጋ እንዳይደርስበና ሌላ ጥይትም በቅርቡ ለማግኘት ስለማይቻል ፣ ሹማምንቶቹ ወዲያና ወዲህ እያሉ እየቆጠቡ እንዲተኩሱ ለየወታደሩ ትእዛዝ ይሰጡ ነበር ።

የሐበሾቹ ጦር ከመካከለኛው ቆቀር በግራ በኩልም ስለ ተጫነ ጀኔራል አልቤርቶኒ ተጠባባቂው ባታ እንዲመጣ አዘዘ ። በዚሁ ጊዜ የአቴጌ ጣይቱ ጦር ስድስት ሐኪንስ **የሚባሉትን መድፎች ይዘው ከተዋጊው 3,000 ሜትር ርቀው መድፍ እየተኩሱ ምንም እንኳን በጣልያኖቹ ላይ ጉዳት ባያበዙ ተዋጊዎቹን ሐበሾች ስለ ደገፋቸው ወደፊት ሁሉም በኪዳነ ምሕረት በር በኩል እየገፉ ይዋጉ ጀመር ። በዚሁ ጊዜ ተጠባባቂው የገባው ባታ ጦር ደርሶ እንደገና ያደረጉት መቋቋም ሐበሾቹን ወደኋላ 1000 ሜትር ያህል እንዲያፈገፍጉ አደረጋቸው ።

በዚህ ዓይነት ፣ ተዋጊው የጦር ሠራዊት ወደፊት ለመግፋት እንዳመነታ ባየ ጊዜ ፣ ቀኝ ሌባሽ የሰበሰበው ፊታውራሪ ገበየሁ ወደ ሰዎቹ ፊቱን አዙሮ ... "የእምባ እሳጊው አሽናፊ ፊታውራሪ ገበየሁ በምን አኳኋን እንደሞተ ወደ ሸዋ በሕይወት የሚመለሱት ይናገሩ" ብሎ ተናግሮ ፣ እንደ አንበሳ ተወርውሮ ወደ ኢጣልያኖቹ መስመር ገብቶ ሲዋጋ ፣ በ3 ሰዓት ላይ በመትረየስ ተመትቶ ኪዳነ ምሕረት አበሩ

* በፊተኛው ዓንድ ወታደር የተሰጠውን 112 ጥይት ብሎ የገበረውን አውን 142 አድርጎታል ።

** Hotchkiss 6 Benjamin Berkley. የመድፍና መትረየስ ሥራን ያመነጨ ሰው ነው ። በፈረንሳይኛ በኩል ወደ ኢትዮጵያ የመጣው መድፍ በርሱ ስም ይጠራል ።

ከነቁጥራቸው ገልጸታል ። የኢጣልያኖቹን እያጋነነ ከነስማቸው ሲያ
ነሣ ፣ የኢትዮጵያን ወገን ከፊታውራሪ ገበየሁና ከደጃች ሜጫ በቀር
እምብዛም አልዘረዘረም ። የዚህም አንዱ ምክንያት ኢጣልያዊ ጸሐፊ
በመሆኑ ብቻ ሳይሆን ፣ በሥፍራውና በጊዜው በስሉሰብት ከሐበሾቹ
ውስጥ እነማን በጀግንነት እንደሞቱ ስማቸውን እየጠቀሰ ሊተ
ርክ አይችልም ። የተዋጉት የኢጣልያ ሹማምንቶችም ፣ የጠላቶቻቸውን
የኢትዮጵያውያንን ስምና ሥራ በዝርዝር ስለማያውቁ ፣ ቢያውቁም በዚ
ያን ዘመን አብዛኛዎቹ ጽፈው ስላላስቀሩት ፣ የኛም ወገኖች ዘርዝር
በያይነቱ የመጻፍ ልምድ ስለሌላቸው ፣ ብዙ አስደናቂ ጀግንነት የሠሩት
ተራ ወታደሮች ፣ የበላይና የበታች አለቆች የብዙዎቹ የጀብዱ ሥራቸ
ውም ስማቸውም እንደ ተቀበረ ቀርቷል ። ቢሆንም የመጀመሪያውን
ግንባር ቀደም ጦር የተዋጉት ራስ መንገሻ የሐንስ ፣ የግሽም ገን
ጉል ፣ ራስ መንገሻ አቲከምና ደጃች ገሠሠ ፣ በጅሮንድ ባልቻና ፊታው
ራሪ ገበየሁ ፣ ደጃች በሻህና ደጃች ሜጫ ፣ አዛዥ አባ ተምሳስ መሆ
ናቸውን ፣ ከነዚህም መካከል በተለይ ሁለቱ ታላላቅ የጦር አለቆች
ፊታውራሪ ገበየሁና ደጃች ሜጫ በዚሁ ጦርነት አስደናቂ የጀብዱ
ሥራ እየሠሩ መሞታቸውን ትውልዱ ኢጣልያዊ የሆነው የኢት
ዮጵያ ታሪክ የሚያውቀው ኮንቲ ሮሲኒ ሳይደብቅ ገልጾታል ።
በአጸጸቱ ከሁለቱም የፊታውራሪ ገበየሁ አባ ጉራን አሟሟት ፣
"ከፊት ያሉት ጭፍሮቹ የማመንታት መልክ ሲታይባቸው ፣ ከሁሉ
እንደ አንበሳ ተወርውሮ በጠላቶቹ ሰልፍ ገባ " የሚል ቃል ጨምሮ
አድንቆ ጽፎላቸዋል ። ሌሎቹም የጦርነቱን ማስታወሻ የጻፉ የኢጣልያ
መኰንኖች የገጠማቸው ራሳ የማዕረግ ልብሱን እንደ ለበሰ ወደኋላ ሲ
ለስ ፣ በምርኮኝነት ተይዘው የነበሩት የኢጣልያ ሁለት የመቶ አለቆች
ጉልየልሞ ፒኒና ቶቶ ማየታቸውን ገበየሁም ከንጉሡ የጉብዝና የጦር
አለቆች ውስጥ አንዱ መሆኑን በማስታወስ ገልጸዋል ።[1]

በዚህ ጦርነት ፣ የራስ መኰንንን ወሳኝ አወጋግ ኮንቲ ሮሲኒ እም
ብዛም አላገነነውም ። ነገር ግን ፣ ምንም እንኳን ራስ መኰንን የዘመ
ቱበት እቅጣጫ በመንኩሲቶ ግንባር ቢሆንም ፣ በፊታውራሪ ገበየ
በኩል የኢጣልያ ጦር በጣም መጫኑን በመገንዘብ የማህሉ የ
ራምንዲ ጦር ስአልቤርቶኒ የደረሰ እንደሆነ አደገኛ ሁኔ
እንዳይፈጠር ሲሉ ካሉበት ሥፍር ወደቀኝ በኪዳነ ምሕረ
ጉብታ በኩል ተቀልብሰው ከአልቤርቶኒ ጦር ጋር በስ
በኩል ሲዋጉ ቀኝ እጃቸውን ተመትተው ወደቁ ። ያቆሰላቸውን

1 Adua.E. Bellavita, P 354. Gli Italiani in Africa, Angelo Del Boca, p
656-692. La Prima Guerra d' Africa R.Bataglia pp. 733-776.



የኢጣልያ መኰንን ልጃቸው ተኛዝማች ይልማ ተኩሰው መግደላ
ቸውን ፣ መኰንንም ከወደቁበት ተነሥተው ቁስላቸውን አስረው
ጦርነቱን መቀጠላቸውን ግራጊታ ኃይለ ጊዮርጊስ በግዕዝኛ ጽሑፋ
ቸው ያመለክታሉ ።[1]

የሆነ ሆኖ ፣ የጦር አቢጋዙ የፊታውራሪ ገበየሁ መሞትና የራስ
መኰንን መቆሰል ሲሰማ በንጉሠ ነገሥቱ ዘንድ ጥርጣሬና ሥጋት
አሳድሮ እንደ ነበርና ጦሩ ወደ ኋላው መሰስ እንዲል ለማዘዝ አስበው
ነበር ይባላል ። ነገር ግን እቴጌይቱም እንዲራስ መንገሻ ፣ እንዲራስ
ሚካኤል ፣ እንዲንጉሥ ተክለ ሃይማኖት በየግንባራቸው ደህና አድርገው
በመመከት እሥጊ የነበረው ሁኔታ ተሻሽሎ በዚህ ፈንታ በመጀመ
ሪያው የጦርነቱ ወቅት አሸናፊነት ያገኘ መስሎት የተደሰተው
ገነራል አልቤርቶኒ ራሱ ተሸንፎ ተማረከ ። የርሱም መማረክ
ወገኖቹን ሲያስደነብር በኢትዮጵያውያን በኩል የድል ሙራ የሚፈ
ነጥቅ መሆኑ እየጠረጠረም ።

1 ዜናው ለልዑል ራስ መኰንን ፣ ገጽ 53 ።



የተማረከው ጄኔራል ማቴዎስ አልቤርቶኒ
ከማዙኮኒ መጽሐፍ

## ምዕራፍ ሠርባ አንድ

### የመጀመሪያው ብርጌድ ጦር ተዋግቶ ስለ መሸነፉ
### የጄኔራል አሪምንዲና የኮሎኔል ጋልያኖ ፍጻሜ

በኢትዮጵያውያን በኩል እንደዚያው እንደ ማልያኖቹ፣ በግራ በኩል የአልቤርቶኒ ጦር በዘመተበት ግንባር የንጉሥ ተክለ ሃይማኖት፣ የእቴጌ፣ የፊታውራሪ ገበየሁና የደጃች ሜጫ ጦር በመጨረሻም የንጉሠ ነገሥቱ ዘበኛ እንደ ዘመተ፣ አሁን በመካከል ዘምቶ ሲዋጋ በምንመለከተው በጄኔራል አሪምንዲ ጦር ፊት ለፊት ለውጊያ የተሰለፉት ራስ ሚካኤልና ራስ ወሌ ናቸው። ይኸም ጦር በጠቅላላ የቤገምድር፣ የየጁ፣ የአማራ ሳይንት፣ የወሎና የአካባቢው መሆን ነው።

ነገር ግን፣ በዋዜማው በየካቲት 22 ቀን ማታ ኢጣልያኖቹ ከም ሽግ ወጥተው ሲሊቁን ተጉዘው ግራና ቀኝ እየተጠባበቁ በጧት በኢትዮጵያውያን ጦር ላይ አደጋ የመጣሉ ጉዳይ በፕላን ስሕተት ወይም ለየብቻ ድል አድራጊነትን በመመኘት፣ ይልቁንም የኢጣልያኖቹ የሌሊቱ ግሥጋሤ በነእውቀትም እግካይነት ባዬ ምንልክ ዘገድ ክሌሊቱ ከዘጠኝ ሰዓት ጀምሮ ስለተሰጣ ከሽፎባቸዋል። በዚህ ምክንያት ሦስቱም ጄኔራሎች ጦርነት የጀመሩባቸው ሰዓቱም ስፍራውም የተለያየ ስለሆነ፣ የግራውን አዝማች የጄኔራል አልቤርቶኒን ጦር በረፋድ ሰዓት ላይ የደመሰሰው የኢትዮጵያ ጦር ወደ ግራው ተቀልብሶ በመካከል ሆነው ለሚዋጉት ለነራስ ወሌ ጦር ተደራቢ ሆኖ የአሪምንዲን ጦር ለማጥቃት የተመቸ ሆኗል።

የአሪምንዲን ጦር ወደ ሰባት ሰዓት ላይ ፈጽሞ የደመሰሰው ጦር በቀኝ በኩል ይዋጋ በነበረው በጄኔራል ዳቦርሚዳ ጦር ላይ ደርሶ እስኪጨልም ድረስ ተዋግቶ መደምሰሱን ወደፊት እንመለከታለን። ይጋግሞም ከጄኔራል ባራቲየሪ በተሰጠው ፕላን መሠረት አሪምንዲ ለአልቤርቶኒ ቢደርስለት ዳቦርሚዳና በኋላ ያለው የጄኔራል ኤሌና ተጠባባቂ ጦር ከአልቤርቶኒና ከአሪምንዲ ጋር ተባብሮ ቢዋጋም፣ በመካከል ለተሰለፉት ለራስ ወሌና ለራስ ሚካኤል በጧት ለተዋጉት ለነ ፊታውራሪ ገበየሁ ጦርም በሌላው የጦር ግንባር ያለው የበረከተው የኢትዮጵያ ጦር ወደነዚሁ በመሰብሰብ መዋጋቱ ስለማይቀር፣

እንጊሊያውም በሦስት በመሥመር የተከፈለውን ጦር ለየብቻ በየተራ በመቀጋትና ጦርነቱ ጧት የጀመረ ላይን እስኪይዝ በመቆየት ፈንታ ድምሩ የኢጣልያ ጦር በድምሩ የኢትዮጵያ ጦር ተሸንፎ ምናልባት ውጊያው ወደ ስድስትና ሰባት ሰዓት ላይ ሳያልቅ አይቀርም ነበር ማለት ይቻላል ። በዝርዝር ተቢታትና ያዘገፈ ያው ጦር በድምር ተዋግቶ ለማሸነፍ የሚከለክለው ነገር ሲኖር እንደማይችል ይገመታል ።

ነገር ግን ፣ ጄኔራል አልቤርቶኒ በኢትዮጵያ ጦር ሰፈር በቀኝ በኩል ከዘመቱት ጓደኞቹ ከአሪሞንዲና ከዳቦርሚዳ ተለይቶ ወደፊት ገሥግሦ ጦርነቱን በመገርመር ተዋግቶ ተሸነፈ ። ተሸንፎም ሲማረክ ይኸን ሁሉ የደረሰበትን አደጋ ባደኞቹ ጄኔራሎችና የበላዩ አለቃው ጄኔራል ባራቲዬሪ እያውቁም ነበር ። ለምሳሌ አልቤርቶኒ ጧት በሚዋጋበት ጊዜ ፣ "እርዳታ ይድረስልኝ " የሚል ደብዳቤ ጽፎ ባንድ ፈጣን ፈረሰኛ እጅ ለጄኔራል ባራቲዬሪ የላከ ጊዜ በርሱ አሳብ ፣ " ደብዳቤው በቶሎ ደርሶ በጦርነቱ ሰዓት የእርዳታው ጦር ይደርሰኛል " የሚል ምኞት ነበረው ።

ነገር ግን ፣ አዛዡና ታዛዡ 55 ማይል ተኩል ከመራራቃቸውና ከመንገዱ ወጣ ገባነት የተነሣ ፣ መላክተኛው ደርሶ የእርዳታው ጦር ከመድረሱ በፊት ባለው ጊዜ ውስጥ ጦሩ ተሸንፎ አልቤርቶኒም ተማርኮ የምተው ሞቶ የተረፈው ከጦርነቱ ጉራ 'እግሬ አውጭኝ' ብሎ የሚሸሸው የጣልያን ጦር በመንገድ ከእርዳታው ጦር ጋር ተገናኘ ። የሸሸት ፣ ጦርነት ካልቀመሱት ጋር ተገናኝተው በአሪሞንዲና በዶጀኑ መሪ በጄኔራል ኤሌና ውስጥ ሆነው እንደገና ባዲስ ኃይል ለመዋጋት ተዘጋጁ ። የጦርነቱን ዝርዝር ታሪክ ኮንቴ ሮሲኒና ራዮልፎ ማፀኮኒ ከጻፉት ላይ ከዚህ እንደሚከተለው ይነበባል ።

> ... የጄኔራል አልቤርቶኒ ጦር ተሸንፎ የተረፈው የነጭና የጥቁር ወታደር እየሸሸ የሸሸው ጦር እያባረረ ፣ የጄኔራል አሪሞንዲ ጦር ወደ አለበት ወደ ዝባን ዳዕርና ወደ ራዓዮ ተራራ ደረሱ ። ...በአሪሞንዲ ውስጥ ለውጊያ የተሰለፉት ክፍተኛ የጦር አለቆች የመቶሌው ጋልያኖ ፣ ቦድዋ ፣ ሺያንቺ ፣ ደስቲፋኖ ፣ ኮምፒያኖ ... ይባላሉ ። እነዚህም የየክፍል መሪዎቻቸውን ይዘው ሲጠባበቁ ሐበሾቹ ከኋላ እየተከታተሉ የነጩንና የጥቁሩን የኢጣልያን ጦር እያባረሩ ደረሱ ። በዚህ ጊዜ የመድፈኛው አዛዥ ሎፍሬዶ መድፎቹን አስጠምዶ ሲተኩስ ሲል ፣ አባራሪዎቹና ተባራሪዎቹ ቅርብ ለቅርብ ስለሆኑ አንዳንድ ጊዜ ተደባልቀው ስለሚዋጉ ደርቦ እንዳይመታቸው ስለፈራ ተኩሱን ማቆም ግድ ሆነበት ... መልሶ ሲተኩስም ፣ አባራሪዎቹ ተኩሱን ሰምተው ተቢታትነው በየሚገኙ በየሸለቆውና በየቁጥቋጦው ገቡ ። በመድፈኛ ተባራሪዎቹን የባንዳ ወታደሮች ለማቆምና ለማዋጋት ተፈልጎ ነበር ። ግን በፍጹም ሊቆሙና አበሾቹን ሊመክቱ አልቻሉም ። የዚህንም ወሬ



ጄኔራል ባራቲዬሪ በሰማ ጊዜ የሚሸሹት ተሰባስበው በራዓዮ ቁልቁለት ላይ እንዲመክቱ ሲል የጦር ጅማሮንት ላከ ።

ከአልቤርቶኒ ጦር የሸሹት የጥቁር ወታደሮች ፣ ለእርዳታ የመጡትን የነጭ ወታደሮች እንዳገኙ ከተጠራቀሙ በኋላ ፣ ወደፊት የሚገቱትን የኢትዮጵያውያንን ጦር ለመመከት ተዘጋጁ ። ነገር ግን በዝባን ዳዕር በኢራራ ጠባብ መንገድ በኩምር ቃጥቃጤ በኩል ያለ የሚልክ ጦር እየገፋ ከብቦ ይመታ ጀመር ። ከዚያ ወደ መተራረብ ደረሱና በውስቱም በኩል ኃይለኛ ጦርነት ተጀመረ ። መድፈኞቹም በሰዓት መቶና በሺ ሜትር ርቀት ሲታኩሱ ፣ የቀረውም [illegible] በየሸለቆው በሩቅም በቅርብም ሆኖ እየተታኮሰ ይዋጋ ጀመር ። ... [illegible] ሉቆ በሳንጃና በጉራዴ በጨበጣ ጦርነት እየተደባደበ መገዳደል [illegible]

በዚህ ጊዜ ፣ የሸዋ ጦር እየበረከተ ሔደ ። በኋላ የሚልከም በደቡብ በኩል የአልቤርቶኒን ጦር ፈጅተው ከጨረሱ በኋላ ፣ በዳዲትና በአባ ገሪማ ተራራ መካከል አልፈው በማይ ቆዳ በኩል ወርደው በአቦ በኩል እኛቅበው ወደ ሰማይታ ወጡ ። ከዚያም ወደ ሰሜን ወደ እዲ በቂ አዘቅዝቀው ግይ ኢንዳም ከሚባለው መንደር ቀመው የማርያም ሸዊቶን ውጊያ በሩቁ ይመለከቱ ጀመር ። በዚያም የንጉሡና የራስ ጦር በሁለት በኩል ተከፍሎ እንደኛው በግንባሩ ያለውን የኢጣልያናዊን ጦር ሲገጥም ፣ የቀረው እየተሽሎከለከ በምዕራብ በኩል በዝባን ዳዕር ያለውን ጦር ገጠመ ። የቀረውም ወደ ቢላህ ተራራ ሔዶ የዳቦርሚዳን ጦር በጀርባ በኩል ገጠመው ። የዝባን ዳዕርን ጉብታ ቀድሞ መያዝ ጠቃሚ መሆኑን ጄኔራል ባራቲዬሪ ተረድቶት ስለነበረ ፣ በቶሎ እንዲይዝ ለኩሉኔል ስቲፋኒ ሁለት ጊዜ ላከበት ። ኩሉኔሉም ይቺን የዝባን ዳዕርን ተራራ ጫፍ ቀድሞ ለሚይዝ ሽልማት እደርግለታለሁ ብሎ ለጭፍሮቹ ተስፋ ሰጠ ። አንድ ወርቅ የሚሆን እነማማሪ ወታደሮች(በርሳሊየሪ) በሌተናና ኩሉኔል ኮምፒያኖና በካፒቴን ተዘበሪ ... እየተመሩ ዳገት ቁልቁለቱን በችግር አልፈው ወደጫፍ ተጠጉ ፤ ዳሩ ግን ጫቱ በሐበሾቹ ተይዞ ተገኘ ። ቢሆንም ኮምፒያኖ 'እየዳችሁ ልጆች ፣ ሓሬ ማታ ኅድዋ ገብተን ከሰ እንበላለን' እያለ ወታደሮቹን ያበረታታ ነበር ። የቀረው የፊጋሮማው አዛዥ አለበት ቦታ ሆኖ ኮምፒያኖ አንዱን ያበሻ ወታደር በሰይፉ መትቶ ቁልቁል ሲወረውረውና ቀጥሎ ብዙ አበሾች እርሱን ከበው ሲገድሉትና ከርሱ ጋር ያሉት ጣልያኖችም በዚያው ቦታ እየተዋጉ ሲያልቁ በሩቁ ይታዩ ነበር ። ስለዚህ በ10:30 (በአራት ሰዓት ተኩል) የተራራው ጫፍ በአበሾቹ እጅ ተረጋግጦ መያዙ ታወቀ ።

የዝባን ዳዕር ጫፍ የአሪሞንዲን ጦር በቀኝ በኩል ለመምታት ባንድ ወገንም አልፎ የዳቦርሚዳን ጦር ለመውጋት ምቹ ስፍራ ስለ ሆነ ፣ የዚህ ጫፍ በአበሾች እጅ መያዝ ለውስቱም ከፍል የኢጣልያ ጦር ፍጻሜ ምልክት ሆነ ። ስለዚህ እዚሁ ስፍራ ሆነው የኢትዮጵያ ወታደሮች በመጀመሪያው ባታተ ጦር ላይ እየተኮሱ ሲመቱ እንደዚሁ ከግራና ከቀኝ ከበው እየተታኮሱ ዋናውን የብሪጌድ ጦር ከተራ ተያያዙት ። የመጀመሪያው ባታተ ጦርም እየተታኮሰ በዝግግንት ሲጋደል ፣ አበሾቹ ቀጥቅጠው ፣ ሲብና ቀጥኝ ተገን እየያዙ እየተጠጉ በመታኮስ ብዙ ጉዳት አደረሱ ። ስለዚህ ጣልያኖቹ ባሉበት ቦታ መከላከል ከንቱ መሆኑን ስለ ተመለከቱ ፣ ማዦር ደስቲፋኖ ወደኋላ እንዲያፈገፍጉ

ሲሸሹ የቀሩት አለቆቡት ። ከርሱ ጋር ከነበሩትም ዐሥራ ስምንት ሹማምንት ያመለጠ አንድ ብቻ ነበር ። እርሱም በዚሁ ጦርነት ሞቶ ተገኘ ።[1]

ስለ ሌተና ኮሎኔል ጋልያኖ አሟሟትም ፣ ወሬው በሦስት ዓይነት ተተርኮ ይገኛል ።

፩ኛ ግምባሩን ቆስሎ ደሙን እያዝለከለከ ፣ "ጌቶች ሆይ ሰዎቻችሁን እንደያዛችሁ ፍጻሜያችንን (እሿሿታችንን) እናሳምር ” ብሎ አጠገቡ ላሉት ሹማምንትና ባንዶች ተናግሮ ወደኋላው ዘወር እንዳለ ፣ ከዚያ ምናልባት ጉብታ እንደ አዘንመና ከዚያ ወዲያ አለመታየቱን እንደ የጦር ሹም ማውራቱ ተጽፎ ይገኛል ።

፪ኛ. መንጋጋውን በጥራ በኩል ተመትቶ ደሙ በጣም ይወርድ ስለነበረ ፣ በትሉውን ይዘው ወደሚጠብቁት አሽከሮቹ ሔዶ ባንድ ድንጊያ ላይ ተቀምጦ ውሃ እምጠላኝ ብሎ ጨርቁን በወሃ እየነከረ ደሙን ለማቆም ሲሞክር የኢትዮጵያ ወታደሮች በድንገት ደርሰው ማረኩት ። ጋልያኖ መሆኑንም ስላወቁ የደሲታ ጥይት ወደ አየር እየ ተኰሱ ጕትተው ወደ ታችኛው ሸለቆ ወሰዱት ። በዚያም ለንጉሣችን እናቀርብሃለን ብለው ሲጕትቱት እርሱም 'የርሱን (የምኒልክን) ፊት አላይም ' ብሎ ሲተናነቅ አንዱ በጥይት መትቶ ገደለው ።[2]

፫ኛ. ማጆር ባቲሲታ አሜሊዮ የሚባለው ለጦር ምክትል ሚኒ ስትሩ በጻፈው ደብዳቤ ላይ ፣ " ካግ ኃይሉ የሚባለውን አሽከር ( ያገር ተወላጅ ወታደር ) በመጋቢት 10 ቀን የእስረኞቹን ወሬ እንዲያጠያ ይቅ ልኬው ስለነበረ ፣ ጋልያኖ ከተማረከ በኋላ የመቀሌን ምሽግ የለቀቀ ጊዜ ፣ ሁለተኛ አልዋጋም ብሎ የነበረውን መሐላ አፍርሶ ሰዎቹን ስለወጋ ጥፋተኛ ነው ብሎ አንድ ሊቀ መኳስ እምኒልክ ላይ ከሶት በጥይት ተደበደበ”[3] ይላል ። አንድ የደራሲው ስም ያልታወቀ የግዕዝ ታሪክ ፣ መቀሌ የነበረው ጋልያኖ ሁለተኛ ወደ ንጉሥ መጥቶ እንዳይዋጋ በመሐላ ከሔደ በኋላ ፣ ተመልሶ መጥቶ ሲዋጋ ተማረከ ማራኪው ወደ ንጉሡ ልውሰድህ ቢለው እምቢ ስላለው ገደለው ” ሲል ባጭሩ ያምድሟልና ይኸኛው ሊታመን ይችላል ።[4]

1 Italia ed Etiopia . . . P. 404.
2 La Giornata di Adua, PP.276—277.
3 Lettere e Diari, . . . P.56.
4 መምህር ጋሊዮ (ጋሊያኖ) ዘገበረ በመቀሌ መዘመራን ከመ ኢይመጽእ ዳግመ ለፀብእ መጽአ ተማህረከ ወበ አበየ ይሑር ቅድመ ገጸ ምኒልክ ንጉሥ ቀተሎ እንተ ማኅረኮ ፣ የኢትዮጵያ ጥናት IES, No. 681, P. 129. (አዲስ አበባ ዩኒቨርሲቲ)





በዓድዋ ላይ የሞተው ጄኔራል አሪሞንዲ
ከግዙኮኒ መጽሐፍ

# ምዕራፍ ዐርባ ሁለት

## የቀኝ አዝማቹ የብሪጌድ ጦር ተዋግቶ መሸነፍ — የጄኔራል ጃሌፕ ዳቦርሚዳ እንቅስቃሴ

ቀደም ብሎ በተደረገው ጦርነት ድል ለተመታው ጦር፣ ግንባር ቀደም ሆኖ የተቀሩን ወታደር ይዞ በእምባ ኪዳን ምሕረት የተዋጋው ጄኔራል አልቤርቶኒ ከተማረከና በመካከል በእምባ ራዮ የዘመተው የጄኔራል አሪሞንዲ ጦር ተሸንፎ ከፈረሰ በኋላ፣ ተጠባባቂ ሆኖ በረቢ አሪዬኒ የነበረው የጄኔራል ኤሌና ወታደሮችና በዋናው አዝማች በጄኔራል ባራቲዬሪ ዙሪያ የነበሩት ከውስጣቸው በከፊል እየተመረጡ ሔደው የተሸናፊዎቹን ዕድል መካፈላቸው ታውቋል። ይኸ ሁሉ ሲሆን፣ በቀኝ በኩል የዘመተው ጄኔራል ዳቦርሚዳ ለብቻው ተለይቶ ወደ ማርያም ሸዊቶ ሔዷል። ጄኔራሉ በሩቅ የተለየት ተኩስ መሰማቱ ባይቀርም፣ በጓደኞቹና በቀረው የጦር ሠራዊት ላይ የደረሰውን የመሸነፍ አደጋ በትክክል ያውቅ አይመስለም።

ለብቻው ተነጥሎ ሔዶ ለመዋጋት የፈለገበትን ምክንያት በኋላ የተነሡ ጸሐፊዎች፣ "እንደ አልቤርቶኒ ብቻውን የኢትዮጵያን ጦር ተዋግቶና አሸንፎ የድል አድራጊነትን ክብር ለብቻው ለመውሰድ ተመኝቶ ነው" ሲሉ ጽፈዋል። ከዚሁ እያያይዘው፣ "ያለዚያ አልቤርቶኒ ወይም አሪሞንዲ በሚዋጉበት ጊዜ ወደኋላ ወደ እምባ ራዮ ወደ ግራው ወደ እምባ ኪዳን ምሕረት ታጠፍ ብሎ ለእርዳታ ቢደርስ ኖሮ የሐበሻ ጦር ሳይሸነፍ አይቀርም ነበር" ብለው እንደ መሰላቸው አመልክተዋል። የቀሩት ደግሞ፣ "በመለገም ሳይሆን በፕላንና በመንገድ ስሕተት ለብቻው ወደ ማርያም ሸዊቶ ተመርቶ ሔዶ አብረውት የነበሩትም የንጭ ወታደሮች አገርና መንገድ የማያውቁ ከመሆናቸውም በላይ በመንገዱ መጥፎነት ከሚካው ብዛት፣ ከሰፍራው ወጣ ትብንት የተነሣ ከመድከም ጋር በሌሊት ጉዞ በስሕተት ወደቀኝ ወደ ማርያም ሸዊቶ ርቆ ሔደ ለብቻው ተዋግቶ ለብቻው ተሸነፈ" ብለው በታሪክ ፊት የስሕተት እንጂ፣ የመለገም ወይም የራስ መውደድ ኃላፊነት እንዳይወድቅበት ተከላክለውለታል። በተለይ የርሱ የልፍኝ እስከልካይ የነበረው ኮሎኔል ቤላቪታ ስሕተቱን በፕላን አሠራር፣ በትእዛዝ አሰጣጥና ዓመራር ረገድ በባራቲዬሪ ላይ አድርጎታል።

የኤሪትሪያና የኢሉና ጦር በሚዋጋበት ጊዜ ፣ እዶጋ ላይ መሆኑን ዋናው አዝማች ጄኔራል ባራቲዬሪ ተገንዝቦ የዳቦርሚዳ ጦር መጥቶ እንዲረዳ ለማድረግ እነ ኮሎኔል ባሴንዛኖን ፣ እንማንገር ሳልባን ዳቦርሚዳን እንዲፈልጉት ልኳቸው ነበር ። ዳሩ ግን ፣ ይህ ጄኔራል ከነጦሩ ርቆ ለብቻው ከመሔዱ የተነሣና ግጉፎ ስፍራ በድል አድራጊዎቹ ኢትዮጵያውያን ስለተያዘ ፣ መላክተኞቹ ብዙ ሰዓት ተንከራተውና ባዝነው እግነው ብለው ተመለሱ ።

በኢጣልያኖቹ ጽሑፍ እንደሚገኘው ፣ ጄኔራል ዳቦርሚዳ በውስጡ ሦስት ሺ ስምንት መቶ ስምንት የጦር ወታደር ፣ ሀሥራ ስምንት መድፍ እንደያዘ ፣ እንደ ጓደኞቹ ሌሊቱን ተጉዞ ሲነጋ ወደ ማርያም ሸዊቶ አትራቢያ እንደ ደረሰ ፣ በያለበት ጦሩን ከተፍፍሉ ያሠማራ ጀመር ። ማጆር ደ ቪቶ የሚባለው የጦር አዛዥ የተቆር ወታደሮች ጦር ጨምሮ ግንባር ቀደም በማድረግ ወደ ማርያም ሸዊቶ ላከው ። በዚህም ጊዜ በእባ አቢል አጠገብ ታፈር ሆኖ ይጠባበቅ የነበረው የኢትዮጵያ ጦር በግድቶት ሆኖ ቁልቁል የሚወርዱትን ጣልያኖች ተመለከተና ከዚያ ራስ መንገሻ ወዳሉበት ወደ ጌራ ሔደ ። በዚያው አትራቢያ በአረር የሸዋ ጦር ስለነበረ ፣ ግንባር ቀደሙ የማጆር ደ ቪቶ ጦር ወደ እምባ ድሪያም አቀበት ሊወጣ ሲል ተኩስ ተጀመረ ። ወዲያው በፍጥነት ተዟሙ ተጋግሎ ይዋጉ ጀመር ። የቆሩት የተቆሩም ፣ የነጨዎም ወታደሮች ባንድነት ሆነው እንደ ጉርፍ የመጡባቸውን የኢትዮጵያውያንን ሠራዊት ገትረው ሲዋጉ ደ ቪቶ ወታደሮቹን ይዞ ሳያስብ ፣ ባዶ መስሎት ድሪያም ጉብታ በተለይ እድግባ ከሚባለው ስፍራ ሲደርስ ራስ መንገሻ (ዮሐንስ) በድንገት ተቀብለው ተዋጉትና ሞተ ። የግንባር ቀደሙ ጦር ቢያልቅም ፣ ዋናው የዳቦርሚዳ ጦር በአራት ሰዓት ተኩል ተኩስ በተጀመረበት ጊዜ ከዚህ እንደሚከተለው ተሰልፎ ነበር ።

በግራ በኩል ፣ 10ኛው ባታሎ በደፎኣስካ አዝማችነት ፣ በቀኝ በኩል በእምባ ድሪያም 6ኛው ባታሎ በፕራቶ አዝማችነት ፣ በታች በኩል 5ኛው ባታሎ በጀርዳና መሪነት ፣ 18 መድፎችም በሸለቆ ውስጥ ተጠምደዋል ። በቀኝ በኩል 14ኛው ባታሎ በሶላር መሪነት ፣ 2ኛው ባታሎ በኮሎኔል አይራጊ የሚመራው ከኋላ ይጠባበቅ ነበር ። ከነዚህም በቀር እምባ አረር ላይ በኢትዮጵያውያን ተከበው ሊያልቁ የነበሩትን ጣልያኖች ያዳናቸው ማጆር ደ አሚቼስ በዚሁ ስፍራ ይገኝ ነበር ።

የዚህን ጊዜና ስፍራ ጦርነት ካፒቴን ኪዩሪቺ የተረከው እንደዚህ ይላል ።

ከአረር ጉብታ መቶ ሜትር የሚያህል ወደታች እንደ ወረደን ተጠባባቂው ጦር በድንገት ወደኋላ ሲያፈገፍግ አየነው ። ደ አሚቼስ



እኛ ወደ ተውነው ጉብታ እንድንመለስ አዘዘ ። በዚሁ መካከል ድንገት ከያለበት ጉር የሚያደነቁር የጥይት ጩኸት ተሰማ ። ኢጣልያኖቹም በዚሁ ጥይት በትር እየተጨፈጨፉ ተረባርበው ወደቁ ።

በዚህ ጊዜ ፣ ጥይቱ ከአኩል ሰዓት በፊት ከለቀቅነው ከቅርብ ስፍራ መምጣቱን ተረዳነው ። ነገር ግን ፣ ከግሩ እርዝማኔ የተነሣ ተኳሾቹን በፍጹም ማየት የተሣነን ቢሆንም ፣ ተሰልፈን የጥይት ተኩስ በሚሰማበት አቅጣጫ እንተኩስ ጀመር ። ዳሩ ግን ፣ ተኩሳችን ፍሬ የሰጠ አይመስለኝም ። በመጨረሻ እምሳ የሚሆን የጠላት ወታደሮች ስላየው ፣ በሳንጃ ተዋጉተው እንዲያባርሯቸው አዝዤ ቀጥሎ በሩጫ ሔጄ እኛንና ወገኖቻችንን የሚለየውን ስፍራ ያዘው ። ከዚያ በስልፍ ሆነን በቅሎቻችንን ከሚጠብቁት ጋር የሚገኙትን ሐበሾች መውጋት ጀመርን ... እነዚህ ሐበሾች ሐሞት (ጉብዝና) ያላቸው መሆናቸውን መካድ አይገባም ። የሚተኩሱባቸውን ጥይት ሳይፈሩ ጭንቅላታቸውን እጉንብሰው ሰይፋቸውን እያወዛወዙ በቅሎዎቹ የታሰሩበትን ጠፍር በጥሰው ለመውሰድ እየሮጡ ሲመጡ እኔው ራሴ አይቻቸዋለሁ ። ብዙዎቹንም እጠገባችን ከደረሱ በኋላ በሽጉጥ ልንመታቸውና ልንገድላቸው ችለናል ። በግራ በኩል ተደብቆ የኛን ጦር ያጭድ የነበረውንም የጠላት ጦር ሞኒና የሚባለው ጉበዝ መኰንን ከጭፍሮቹ ጋር ገጥሞ በሳንጃና በጩበጣ ተዋግቶ ካሉበት አስወጥቶ ሲያባርር እርሱ ራሱ ተመትቶ ወደቀ ።

ቢሆንም ባለንበት ስፍራ ለመቆየት ከየአለበት በጡሪያችን በብዛት የሚተኮሰው ጥይት አላስቻለንም ። እኛም ቢያቅጣጫቸው መልሰን ብንተኩስ አልሆነንም ። በዚህ ጊዜ አዝማቹ ማጆር ዳሌበት በኩል 'እየምሸጋችው' የሚል ጩኸት ስለተሰማ ፣ በየቁጥቋጦውና በየቋጥኙ ውስጥ አልፈን እንዲት ቤተ ክርስቲያን አጠገብ ደረስንና የቤተ ክርስቲያኑን ቅጥር እንደ ምሽግ ተገን ይዘን ተቀመጥን ። ይሁን እንጂ በዐጦር ይቂታ ውስጥ 150 ወታደሮችና 3 መኰንኖች አለቁብን ። ... ምሽግ ይዘን ትንሽ እንደ ተንፈስን ጠላት እያደር በብዛት እየተኩሰ እያየነው ይከበን ጀመር ። እንጣጥረን ለመተኮስ የምንችለው የጥይት ጩሱ በሚታይበት በኩል ብቻ ነው ። ... የትግሬን ጦር የያዙት ራስ መንገሻና ራስ አሉላ በአዲ ፈቂ በራዕድ በረቢ አሪቁኒ ያለው ጦር ለእርዳታ ሳይመጣላቸው ጦርነቱን እንዳይጀምሩ ትእዛዝ ተቀብለው ነበር ። የተጠበቀው የእርዳታ ጦር ከአራት ሰዓት ጀምሮ በብዛት ከመጣላቸውና የኢጣልያ መድፎች መምታት ከጀመሩ ወዲህ ዋናው የሸዋ ጦር የዳቦርሚዳን ጦር በኃይል ገጠመው ። የመድፉ ድምፅ ከቀሰቀሳቸው ወዲህ በእባ አቢል በግራ በኩል የጠላት ሠራዊት በብዛት ተገኝቶ በብዛት እየተኩሰ የኢጣልያኖችን የእግረኛ ጦር ከተፍ ፈጀው ። ኢጣልያኖቹ እታች ሆነው ወደላይ ወደ አበሾቹ የተኮሱት ምንም ያህል ጉዳት አላደረገም ። ይልቅስ ሀሥራ ስምንቱ መድፎች የጥይት ነበልባላቸውን እየተተፉ ጠላት የያዘውን ስፍራ ማስቸገራቸው ግልጽ ነው ። በዚህ ሰዓት ዋናው የዳቦርሚዳ ጦር በሙሉ ጦርነቱን ጀመረ ። ... ወታደሮቹም ሹማምንቱም ዋናው አዛዥም ፣ ምንም እንኳን አንድ ታክቲክ (የጦር መላ) ቢጐድል ደንበኛ የጦርነት ሞያቸውን አሳዩ ። በነርሱም ብርታትና በጺ ጠላት እየለየ ለመምታት

. . . ነገር ግን ሺዎቹ ከሃሉበት እየተኛጉ ደጉዱ ስለ ወረዱና ማጥቃታቸውን ስላጠነከሩ ምንም ማድረግ አልተቻለም ። በዚያን ጊዜ ዳቦርሚዳ ሌላ የምናተርበው ተጠባባቂ ጦር እንዳለ ጠይቶኝ አለመኖሩን ባስረዳው ወደኋላ መመለስን (ሽሽትን) አዘዘ . . ጄኔራሉ ራቁ እዝ ዷል ፤ መናገርም አልቻለም. . . በሽሽት ጊዜ በመንገድ ሰው ውሉ ተጨናንቆ እንዳንድ ራሳና ቁስለኛ እየረገጠ የሚያመልጥ ግግቹ ስሁለት ወይም ለሦስት የጋማውን ከብት የተቀመጠ እንዳንዶቹ በራሳቸው መሐድ ያቃታቸው የከብቱንም ጭራ እየጐተቱ የሚራመዱ ነበሩ ። በዚህም ጊዜ ከኋላ እየተተኮሰበት አንዳንዱ ይወድቃል . . . ቀበሌው ውሉ በጠላት ቁጥጥር ውስጥ ስለሆነ ፣ ሁሉም ራሱን ለማዳን በሚሸሽበት ጊዜ ወደኋላ የነበረው ጄኔራሉ (ዳቦርሚዳ) ጠፋ ። . . . እኔም ወደ ኋላ ተመልሼ ብፈልገው አጣሁት ። ሺዎቹም ለድሉ እርግጠኛ ስለሆኑ ጥይት ስላስቀባቸው ይሁን ወይም ስለደከማቸው የማሳደዱን ነገር ትተው ራሣና ቁስለኛ ይገፉቱ ግግቾችም ምርኮኛ ይሰበስቡ ጀመር ። ጊዜው መሸ ። ከዚያ እንደምንም በየሸለቆው የሞተውን ፣ ከቱኛ የቆሰለውን አስፈን 300 የምንሆነው በመጋቢት 4 ቀን (ኢ.ኤ.አ.) እዲ ቀይሀ ገባን ። 1

ስለ ጄኔራል ዳቦርሚዳ አሟሟት ከጦርነቱ በኋላ ተማርኮ አዲስ አበባ የነበረው ጄኔራል አልቤርቶኒ ለቤተሰቦቹ በጻፈው ማስታወሻ ላይ ፣ "የጄኔራል ዳቦርሚዳን በጦርነቱ ላይ መሞት የራስ ሚካኤል ሹማምንትና በኋላም ራስ መኰንን ከአድናቆት ጋር እንዳረጋገጡለት ፣ የሰላሙ ውል ከተፈጸመ በኋላ ፣ ምኒልክ ሻምላውንና ያንገት መጠምጠሚያውን 'ለቤተ ሰቡ ስጥለት' እንዳሉት ፣ ስለአሟሟቱ ደግሞ ወደ ማታ መቶ ከሚሆኑ ተራፊ ጣልያኖች ጋር ባንድ ጉብታ ላይ ሆኖ እየተታኮሰ በጠላቶቹ ላይ ጉዳት ሲያደርስ ቱርክ ባሻ (ታምሬ) ከኋላ ካለው ከፍተኛ ቦታ ሆኖ እንጣጥሮ ከመታውና ከጣለው በኋላ ሮጦ ሔዶ እንደ ገፈፈው ፣ ጥሩ አድርጎ ፈረንጣይኛ የሚናገረው ግራዝማች ዮሴፍ አጫወተኝ" [2] ሲል ያረጋግጣል ።

በዚህ ዐይነት ፣ የዳቦርሚዳ ገዳይ በትክክል መጠሪያ ስማቸው ባይጠቀስም ቱርክ ባሻ ታምሬመ ሆናቸው ነው ። ምናልባት በኮንቲ ሮሲኒ ጽሑፍ በስሕተት ባሻ ገብሬ ያለው ቱርክ ባሻ ታምሬ ለማለት ይሆናል።

1 Adua, E.Bellavita, PP. 380—390.
2 Lettere e Diari . . . P.80 .





በዓድዋ ጦርነት ላይ የሞተው ጄኔራል ዳቦርሚዳ
ከማዙቦኒ

## ምዕራፍ ዐርባ ሦስት

### የዳግማዊ ምኒልክ ከሙሉ ግንባር ወደ ሠፈር መመለስ

ከዋናው የዓድዋ ጦርነት ወዲህ እስካሁን በዝርዝር የተመለከት ነው ፤ በጽሑፍ ማስረጃ እንዲደልብ የሚገኝበትን የኢጣልያኖችን ወገን ነው ። ምንም እንኳን ሰነድ ያነሰና የተበታተነ ወይም በዘመኑ ተዘርዝር በመታተም በደንብ ለጊዜያችን ያልተላለፈ ቢሆንም ፤ በመጠኑ ጸሐፊ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴ ፤ ግራዝማች ዮሴፍና ነጋድራስ አፈወርቅ በየመልኩ የተዉልን ማስታወሻ መሠረታዊ ሰነድ ነው ። በተለይ የንጉሠ ነገሥቱ አስተርጓሚ የነበሩት ግራዝማች ዮሴፍ በጦርነቱ ቦታ ተገኝተው ለሞንዶን ቪዳቶ በራፖር መልክ ያስተላለፉት ጽሑፍ ከዚያ በፊት ያልታተመ በመሆኑ በመጠኑ ዝርዝር አሳብ ስላለበት በታሪክ ፊት ጠቃሚነቱ ግልጽ ነው ።

በዚህ ሰነድ ውስጥ ግራዝማች ዮሴፍ ፤ በመሠረታዊውና በታሪካዊው ጽሑፍ ውስጥ አገራቸው ትግሬ መሆኑንና የደጃች አርአያ ዘመድ መሆናቸውን ጭምር ጠቅሰው ማጆር ሳልሳን ለእርቅ ከአሥመራ ወደ እንትጮ ሲመጣ ከፊታውራሪ ደሳለኝ ጋር ሔደው መቀበላቸውን ያረጋግጣሉ ። እኚህ ሰው ከቀድሞ ጀምሮ ዐፄ ምኒልክን ባስተርጓሚነት ያገለገሉ ከመሆናቸውም በላይ ፤ ከወንድማቸው ከጊዮርጊስ ንጉሤ ጋር ወደ አሰብና ወደ ኤደን እየተመላለሱ በመሣሪያ መሰብሰቢያው ጊዜ ሲሠሩ ቆይተው እንደዚሁም በውጫሌው ውል በተነሣው ሰፊ ክርክር ሁሉ ከራስ መኰንን ጋር ተካፍለዋል ።

እኚሁ ሰው ራስ መኰንን ፤ የኢጣልያን አገር የጐበኙ ጊዜ ከተከታዮቻቸው ውስጥ ብዙዎቹ በዘመኑ አነጋገር የራስ ሎሌዎች ሲሆኑ ፤ ግራዝማች ዮሴፍ ብቻ በቀጥታ ያፄ ምኒልክ አስተርጓሚና ሎሌ ናቸው ።

እሁንም ግራዝማቹ ፤ በጦርነቱ ሰዓት ከንጉሠ ነገሥቱ ምን ጊዜም ሳይለዩ በዋናው ሥራቸው ባስተርጓሚነቱ ላይ የጦርነቱን ሁኔታ እየጻፉ ፤ አዲስ አበባ ላሉት ለሞንዶን በማስተላለፍ በነርሱም አማካይነት በፈረንሣይኛ ጋዜጣ እንዲታተም ማድረጋቸውን ከመቀጠል አላረፉም ። ከዚህ በፊት እንደ ጠቀስነው ፤ የርሳቸው ጽሑፍ በኛ ዘንድ ያለው ጠፍቶ ሊገኝ የቻለውም የጻፉለት ሙሴ ሞንዶን አዲስ አበባ

በነበረበት ጊዜ ከንጉሠ ነገሥቱና ከየመኳንንቱ የተጻጻፏቸውን ደብዳቤዎች በማኅደር አጠራቅሞ ከኢትዮጵያ ከወሰዳቸው ከሌሎች መጻሕፍት ጋር ለፓሪስ ቤተ መጻሕፍት የሰጠውና በቁጥር 82 ተመዝግቦ የተቀመጠው ነው ።

ዳግማዊ ምኒልክ ፣ ካህናትና ሴቶች ሳይቀሩ ባንድነት አስተባብረው ኢትዮጵያውያንን ባንድ እግር አቁመው ፣ በአገር ወራሪ ፊት አሰልፈዋል ። ቀኑን ሙሉ በማዋጋት ይኸን ዓለም የተደነቀበትን ድል ባገኙበት ማታ ወደ ሰፈራቸው ሲመለሱ ፣ እዲ ፈቂ ጉታ ላይ ወጥተው በእንዳ ሰንበት ቤተክርስቲያን ገብተው ይኸን ድል ለሰጣቸው እግዚአብሔር ምስጋና አቅርበዋል ። እዲ ፈቂ በእንዳ ኪዳነ ምሕረት በመነከሴይቶ ተራራ መካከል የሚገኝ ነው ። የእዲ ፈቂም ተራራ ከባሕር ከፍታው 2062 ሜትር[1] ነው ። ከሌሎቹ አብያተ ክርስቲያናት ወደዚህ መሔድን የመረጡት ምናልባት ጦርነቱ የተደረገው የካቲት 23 ቀን እሑድ ስለሆነ ፣ የእዲ ፈቂ ቤተ ክርስቲያን እንዳ ሰንበት (የሰንበት ቤተ ክርስቲያን) ስለሆነ ፣ 'ዕለተ ሰንበት የሰቀለት ቀናኝ' በሚል እምነት ይሆናል ።

ከዚያ ወርደው ሠራዊቱ ፣ "እየገደለ ሰጠው ላሞራ! " እያለ በሆታ እያጀባቸው ፣ በደስታና በእልልታ ወደ ሰፈራቸው ደረሱ ። ወደ ድንኳናቸው ገብተው በዙፋናቸው እንደ ተቀመጡ ፣ ጦርነቱን እንደ ወንድ በትጋት የተካፈሉት የሚወድዋቸው ባለቤታቸው እቴጌ ጣይቱ በኢትዮጵያ ልማድ ለገዢና ፣ ለንጉሥ እንደሚደረገው ሁሉ ንጉሠ ነገሥቱ ወደ ተቀመጡበት ዙፋን ቀርበው ፣ እጅ ነሥተው የድል አድራጊነት ምልክት የሆነውን የወርቅ ሎቲ በጆሮአቸው አንጠለጠሉላቸው[2] ።

በማግሥቱም ፣ በዓድዋና በአክሱም ዙሪያ ያሉ ካህናት ለድሉ በዓል ተሰብስበው ነበርና ምራቁ በቅድሚያ ለአክሱም ካህናት ሰላ ተሰጠ ፣ ካህናቱ ከድጓ ውስጥ "ሞያ ለሞት ሰዓር ለጣኦት ወገብረ ትንሣኤ በሰንበት"[3] የሚለውን ጥቅስ ገሥው አዜሙ ። ምስጋናም "አንተ ቀጥቀጥከ አርእስቲሁ ለከይሲ ወትሁቦሙ ሲሳዮሙ ለሕዝበ ኢትዮጵያ" የሚለው ከዳዊት መዝሙር ተዘመረ ።

1 Guida dell' Africa Orientale, P.224.
2 Storia di Etiopia ,Conti Rossini, P.449
3 የድጓው ትርጉም "ሞትን አጠፋ ጣኦትንም ሻረ ፣ በሰንበትም ትንሣኤ አደረገ" [illegible] ምዕ.1 ቁ. 10 ፣ ምዕ.2 ቁ. 14



በአዲስ አበባ ገና የጦርነቱ ወሬ ሳይሰማ ውጊያውና ድሉ በተፈጸመበት ቀን የጊዮርጊስ ለት የቤተ ክርስቲያን አለቃ መምህር ጸጌ የሚባሉት ሊቅ የተቀኙት መወድስ ቅኔ እንደ ትንቢት ሆኖ ተደንቆላቸዋል ። ቅኔው ታሪካዊ ስለሆነ እንደሚከተለው አስፍረነዋል ።

በሕፅነ ምኒልክ ይረፍቅ ሰማዕተ ልዕልና
ወበሕፅነ ሰማዕት ይትሐወስ አሰረ ምኒልክ ላዕክ
እስመ እም ርምያ ፈተተ አድባረ ደንጋጌ ወሀውክ
ምኒልክ ንጉሥ አድኅና ዘኢየርር መልእክ
ወእግረ ምኒልክ ኢይትሐወክ
እስመ በቅድሜሁ የሐውር ጸያሔ ፍኖት ወልደ እምላክ
ቡርክትኪ ገነተ ጸጌ እስመ ውእቱ ቡሩክ
ዓለመ ምኒልክ ቀዳማዊ ዘይመጽእ ምኒልክ
ወስሉቅ ሶርያ ትሰግድ ወታስተብርክ
በጽባሕ እስመ ቀርበ መስና ርምያ መሥዋዕተ ሠርክ[1]

በሙሉ ሁሉን መተርጐሙ ምንም ያህል ስለማይጠቅም ፣ ከሙሉው አንዳንዱን ፍሬ ነገር ግዕዝ ለማያውቁ እናብራራለን ። አምስተኛውና ስድስተኛው ሐረግ ፣ "ወእግረ ምኒልክ ኢይትሐወክ ። እስመ በቅድሜሁ የሐውር ጸያሔ—ፍኖት ወልደ እምላክ" "መንገድ ጠራጊው ወልደ እምላክ በፊቱ ስለሚሔድ ፣ (ምኒልክ እርምጃ አይደናቀፍም" ማለት ነው ። ወልደ እምላክ የራስ መኰንን የክርስትና ስም ስለሆነ ፣ መኰንን ግንባር ቀደም ጦር አዝማች እየሆኑ በአላጌና በመቀሌ እየተቀደሙ ለንጉሠ ነገሥቱ የጦርነት ጉዞአቸውን ያቀኑትን ለመጥቀስ ነው ።

ከሁሉ የቅኔ ሐረጉች የመጨረሻው መስመር ፣ "በጽባሕ እስመ ቀርበ መስና ርምያ መሥዋዕተ ሠርክ" "የሮማ ጥፋት እንደ ዕለት መሥዋዕት በጧት ቀርቧል" ያሉት ለባለቅኔው እንደ ደንበኛ ትንቢት ተቆጥሮላቸዋል ። በእርግጥም ግንባር ቀደም ሆና በጧት ግጥሚያ ደርሶ የተማረከው የጄኔራል አልቤርቶኒ ጦር የተመታውና የኢጣሊያ ጦር ቅስሙ የተሰበረው ከጧቱ ላይ ስለሆነ ፣ "በጽባሕ እስመ ቀርበ መስና ርምያ . . ." ብለው የጦርነቱ ዕለት የጦርነቱን ወሬ ሳይሰሙ የተቀኙትና በተግባር የተፈጸመው በትክክል ተገናኝቷል ። አዲስ አበባም እንደገቡ ዐፄ ምኒልክ ይኸንን ሰምተው ሸልመዋቸዋል ይባላል ።

1 መጽሐፈ ቅኔ [illegible] ገጽ 255

## ምዕራፍ ዐርባ አራት

### በዐድዋ ጦርነት ከኢትዮጵያ ወገን የሞቱትና የቆሰሉት

የኢትዮጵያውያንን ጀግንነት ፣ አንዳንዶቹ ጣልያኖች ሲያደንቁ አብዛኞቹ በከንቱ ለማስተባበል ይሞክራሉ ። ሲጀመር የተገላቢጦሽ የነርሱን የተሸነፉትን አንዳንዱን የጦር መኰንኖቻቸውን ፣ "በጀግንነት ተዋግቶ ሞተ ፤ እንዲሁን የመሰለ አርበኛ በሚያስደንቅ አኳኋን እየተዋጋ ወደቀ" ሲሉ ፣ የኢትዮጵያውያንን ጀግንነት ግን ፣ "እንደ አውሬ እየተጯጯሁ መጡብን ፤ ሬት ለሬት ጉራጁ መሣሪያ ከመድፋችን ላይ ሲወድቁ ዐይን የላቸውም" በሚል ማጥላላት ባለበት አነጋገር ሲገልጹ ይፈልጋሉ ። በተቃርኖ በኢትዮጵያውያን ጀግንነት ተሸንፍን ማለትን በመሰቀቅ የተሸነፉበትን ሰበብ ወደሌላ አቅጣጫ እየመሩ ፤

፩ኛ. የጀኔራል አልበርቶኒ ግንባር ቀደም ጦር በጥዋት የተመደበለትን ሥፍራ አልፎ ስለዘለቀ ፤

፪ኛ. አልበርቶኒ በሚዋጋበት ጊዜ ሌሎች ዳቦርሚዳና አሪሞንዲ ለየራሳቸው ድሉን በመመኘት ለእርዳታ ሳይደርሱለት ስለቀሩ ፤

፫ኛ. ከአገር ተወላጅ በቁጥር የሚበልጡት የነጭ ወታደሮች በተለይ በቅርብ የመጡት በማያውቁትና ወጣ ገባ በሆነ መንገድ በሌሊት ጉዞ ስለደከሙ ፤

፬ኛ. በወታደር ቁጥርም ፣ የኢጣልያን የወታደር ቁጥር የኢትዮጵያ አራት ጊዜ ስለሚበልጠው እያሉ ልዩ ልዩ ምክንያት መስጠታቸውን ባለፈው ተመልክተነዋል ።

በጦርነትም ሆነ በስፖርት የውድድር ሜዳ የተሸነፈ ወገን ፣ ሁልጊዜም ምክንያት አያጣምና ሊያስደንቅ አይገባም ። ቢያሸንፉ ኖሮ ይኸ ሁሉ አሁን የተሰጠው ምክንያት ይቀርና ሌላ የጀግንነት ልዩ ስም እየተሰጠው ድል የማድረጋቸው ዝና ከበቂ በላይ በተጋነነ ነበር ።

እንደ እውነቱ ከሆነ ፣ በቁጥር የኢትዮጵያ ወታደር ቢበልጥም በዘመናዊና በጠቅላላ የጦር ትምህርት ዕውቀት ኢጣልያኖቹ ስለሚበልጡ ፣ በቁጥር ማነሳቸውን ያላቸው ሥልጣኔ ሊከፍለው በቻለ ነበር ።

ቢሆንም ብዙ የኢጣልያ የጦር መኰንኖች ከጄኔራሎቻቸው ጋር በጀግንነት እየተዋጉ መሞታቸውን ማንም ሊክድባቸው አይገባም ። በዓድዋና በአካባቢው ፣ በየሜዳውና በየሸለቆው የተረፈረፈው ሬሣ ራሱ ምስክር ነው ። ጀግና ከሁለቱም ጦር ሠራዊት ውስጥ መኖሩን ሳንዘነጋ ፣ ይኸን ስመ ጥር ድል ያወረሱን ያባቶቻችን ጀግንነት ምንጊዜም የሚረሳ አይደለም ። በውጊያው ላይ የኢትዮጵያ ሕዝብ ተካፋይ ሆና የሕይወቱን መሥዋዕትነት በመክፈል አንጸባራቂ ድል አግኝቷል ።

እያንዳንዱ ጀግና ግዳጁን በሚገባ ባያከናውን ኖሮ ይህ አኩሪ ድል ባልተገኘ ነበር ። ከሞቱትና ከቆሰሉትም ውስጥ የማናውቃቸው ስለሚበዙ ፣ ስማቸውንና ዝብዲቻቸውን ለትውልድ ለማስተላለፍ ብንመኝም አልሆነልንም ። ቀድሞውን በዘመኑ በማስታወሻ ስላልተላለፈና በዚያን ዘመን ጦርነቱን የተካፈሉት በሕይወት ስለሌሉ እንደዚሁ መቅረቱ ያሳዝናል ። በጀግንነት ከሞቱት መካከል ያንዳንዶቹን በተለይ የመኳንንቱን ጸሐፊ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴ በተዉልን መጽሐፍ ላይ ስማቸውና አሟሟታቸው ባጭሩ የተጠቀሰው ከዚህ ቀጥሎ ያሉት ናቸው ።

ሀ/ ደጃች በሻህ አቦዬ ፣ የፈረስ ስማቸው አባ ደፋር ይባላል ። የዐፄ ምኒልክ እህት የወይዘሮ እያሁሉሽ ልጅ ፣ የንጉሥ ሣህለ ሥላሴ የልጅ ልጅ ፣ የንጉሥ ወልደ ጊዮርጊስና የደጃች ለማ አቦዬ ወንድም ናቸው ። ባገልግሎት ከወንድማቸው በኋላ ፣ ንጉሥ ከተባሉት ከራስ ወልደ ጊዮርጊስና ከነራስ መኰንን እያንሱም ። ምናልባት እንደዚህ ዝንባሌያቸው ወደ አስተዳደር ጭምር ሲሆን ፣ በሻህ መንፈሳቸው ፍጹም ወታደራዊ ይመስላል ። ታናሽ ወንድማቸው ወልደጊዮርጊስ ራስ ሲባሉ የርሳቸው በደጃዝማችነት መቆየት ሰበቡ ይኸው ይሆናል ።

በ1870 ዓ. ም. ዐፄ ዮሐንስ ወደ ሸዋ ዐፄ ምኒልክን ለማስገበር የመጡ ጊዜ ካፄ ምኒልክ አሽከሮች ጠና ጠና ያለው ፣ "ዛሬ ዐፄ ዮሐንስን በጦር ትግቶ እንችልምና አሁን ገብረን እኛም ወደፊት መሣሪያ ሰብስበን በሚመች ጊዜ እምቢ እንላለን" ሲል ፣ እንደ በሻህ አቦዬ ያሉት ጉበዛዝቱ የጦር መኰንኖች "እንበለው!" እያሉ ይፎክሩ ነበር ። በቀጠሮም ጊዜ ፣ "ካፄ ዮሐንስ ጦር ኃምሳ ባለሰናድር ማርኬ እመጣለሁና ተቀበለኝ" የሚል ኖሯል ። በዚያው ሰሞን የዕርቁን ጉዳይ ለመጨረስ ደጃች ናደው በሚመላለሱበት ጊዜ ደጃች በሻህ አቦዬ ያፄ ዮሐንስ ሠራዊት በሜዳ ላይ ሲጓዝ አይተው እልህ ይዟቸው ፣ "በማን አገር ሜዳ እንዲህ ሆነህ ትጓዛለህ" ብለው በፈረስ ጋልበው ሔደው አንድ ባለ ቀሚስ ገድለው ተመለሱ ። በዚህም ምክንያት ፣ "ለሃምሳ ሰናድር



ዋስ የጠራችሁ ፣ በሻህ አቦዬ ከፈለላችሁ" ተብሎ በሰንጉ ምት ተገጥሞላቸዋል ።

ከነራስ ጎበና ፣ ከነራስ ወልደ ጊዮርጊስ ጋር ዳር አገሩን እያቀኑ በግራኝ ወረራ ምክንያት ተንጣጥለው በየባላባቶቻቸው እየተገዙ ይኖሩ የነበሩትን አውራጃዎች እንደገና ለማዋሐድ ዐፄ ምኒልክ በሚያደርጉት ዘመቻ እርሳቸውም ከመጀመሪያዎቹ ጋር ሆነው የከፋንና የጌራን ሕዝብ በማሳመን ወገን ከወገኑ እንዲደባለቅ አድርገዋል ። በዚሁ ምክንያት ፣ ደጃች (በኋላ ንጉሥ) ወልደ ጊዮርጊስ ሲሾሙ ፣ ደጃች (ራስ ቢትወደድ) ተሰማ ናደው ኢሉባቦርን ሲያስተዳድሩ ፣ ደጃች በሻህ አቦዬ ጌራና ከፋ ተሰጥቷቸው ነበር ። ስለዚህ የደጃች በሻህ አቦዬ አንዱ ጉብዝናቸውን የሚያመለክተው በዚያን ዘመን ከነበሩት ከደጃች ኃይሌ እንዳርጋቸው ጋር በማመሳሰል ፣ "ከጉበዞቹ የምናውቃቸው በሻህ አቦዬ ፣ ኃይሌ እንዳርጋቸው" ተብሎ የተገጠመላቸው ነው ።

የበሻህን ሞት እቴጌ ጣይቱ ሰምተው በሐዘን እንዳለቀሱላቸው ጸሐፊ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴ ጠቅሰው ከዚሁ በማያያዝ ስለደጃች በሻህ አቦዬ አሟሟት ፣ "ታላቅ የመኰንን አርበኛ የንጉሠ ነገሥቱ ያክስትዎ ልጅ ደጃዝማች በሻህ የፈረሱ መሬ አባ ደፋር ተብሎ በውነት ስሙ የተጠራው ... ካልጋ ወርዶ ከበቅሎ ላይ ፣ ከበቅሎ ወርዶ ከፈረስ ላይ ሆኖ ተቀማጥሎ ያደገው ባለመጣበር ፈረሱን ሐያ ሁለት ቃዳ መሬት የሚራመደውን ለጓሚ* ይዞበት ባንድ ወገን ሔደ ። በእግሩ ሲሮጥ የወታደር ፈረስ ተውሶ ከአባራሪ ላይ ወደቀ" [1] ሲሉ በራሳቸውና በዘመኑ አነጋገር ገልጸውታል ።

ስለዚህ ፣ ጦርነቱ እንደ ተጀመረ ከመድፉና ከጠበንጃው ተኩስ ብዛት የተነሣ ግርግር ሆኖ በግርግሩ ላይ የጭናቸውን በመጣበር ያጌጠውን ፈረሳቸውን የያዘው አሽከር ባንድ ወገን ሔዶ ስለጠፋ ፣ በግራቸው ሲሮጡ አንድ ወታደር ምናልባትም ከጭፍሮቻቸው አንዱ ሊሆን ይችላል ፣ ፈረሱን ሰጥቷቸው በርሱ ላይ ተጋብተው እያባረሩ ጠላትን ሲወጉ ተመትተው ወደቁ ። ተዋግተው የሞቱት ከጄኔራል አልቤርቶኒ ጦር ጋር በእምባ ኪዳነ ምሕረት ላይ በተደረገው ጦርነት ነው ። በርሳቸው ሞት የተናደዱ ጭፍሮቻቸው በቁጭት ብዙ የኢጣልያ ምርኮኛ ገደሉ ይባላል ።

---

* ለጓሚ ማለት በቅሎ ወይም ፈረስ እየጫነ ፣ እያራገፈ ፣ እየቀለበ የሚኖር ተከታይ አሽከር ነው ። ከዘመኑ የመኳንንት ሹፌር ጋር ሊመሳሰል ይችላል ።

1 ታሪክ ዘመን ዘዳግማዊ ምኒልክ ፣ ገጽ 266

እስፋው ወሰን ምግዜት የነበሩት ናቸው ። እንደነፊታውራሪ ገበየሁ ሳይ ምኒልክ የቆዩ የጦር መኰንን ናቸው ። በ1881 ዓ.ም. ሚሜን ይገዙ እንደነበረ በኢጣሊያኖች ማስታወሻ ይገኛል[1] ። የወሰጋ ገዥ ባሉ በዐፄ መሠረት ጦራቸውን አስከትተው አዲስ አበባ ከገቡ በኋላ ፣ በራስ መኰንን ጦር ውስጥ ግንባር ቀደም ሆነው የአዳጊን ጦር ተካፍለዋል ። የዓድዋ ጦርነት ዕለትም ነት ከነፊታውራሪ ገበየሁ ጋር ተካፍለዋል ። የዓድዋ ጦርነት ዕለትም እንደነፊታውራሪ ገበየሁ ጭት በተደረገው ውጊያ ላይ በጀግንነት ወድቀዋል ።

ሠ/ ቀኛዝማች ታፈሰ ዓባይነህ ፣ የፈረስ ስማቸው አባ ትንታግ ነው ። በዓድዋ ዘመቻ ዕድሜያቸው 25 ዓመት ነበር ። በዕድሜ ወጣት ቢሆኑም ጀግንነታቸው ከፊታውራሪ ገበየሁ ጋር በመጠኑ ተመሳሳይ ነው ። በግዛታቸው በግረቆ ሲኖሩ በአደን ስሙ ገኑ ስለነበሩ ወደ አዲስ አበባ በመጡ ቁጥር የዝሆን ቀንድ ለንጉሠ ነገሥቱ ያቀርቡ እንደ ነበር ፣ በውጊያ ጦርጦሩ ወታደር ፣ ለሁሉ ሥራ ከተፎ ሥል ጡን ስለነበሩ ላስቸጋሪው ሥራ ሁሉ ዐፄ ምኒልክ "ታፈሰን ጥሩ" ይሉ እንደነበር ፣ ብርታታቸውንና ጠንካራነታቸውን እያዩ "ይሞትብ ኛል" እያሉ ንጉሠ ነገሥቱ እጅግ አጥብቀው ይሳሱላቸው እንደነበረ ጸሐፊ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴ በመጽሐፋቸው ጠቅሰዋል ። በአዳጊ ጦርነት በከፍተኛ ጀግንነት እንደ ተካፈሉ ተመልክተናል ። በዚሁ ጦርነት ሃምሳ የሚሆኑትን ጣልያኖች ባንድ ጕራዴ እንደ ጨፈጨፉ ፣ አንድ ላይ ቆመው የተኰሱት አይር (ቀስሀ) እንደ አርበሜ (ኩይስ ቆልል) እንደ ተቆለለ ፣ በእሁን በዐድዋ ጦርነት ስሞን መንድር ይዘው ከጭፍሮቻቸው ጋር ወደፊት እየዘለቁ በየተራራው ላይ ሆነው የኢጣ ልያኖችን ከምሽግ መውጣትና አለመውጣት ቃፊር ሆነው በመጠባበቅ አንዳንድ ጊዜም በርከት ብሎ ከወጣ የንጭና የባሻ ብዙቅ ወታደር ጋር ተገናኝተው በመዋጋት ግዳይ ላዩ ምኒልክ ይጥሉ እንደነበረ ጸሐፊ ትእዛዙ አመልክተዋል ። ከዚሁ አያይዘው የኢጣልያኖቹን ከምሽግ መውጣት በመጀመሪያ ለንጉሠ ነገሥቱ በፈረስ ጋልበው ያስረዱ እርሳቸው እንደነበሩ ከገለጹ በኋላ ፣ የዓድዋ ጦርነት ለት ስለ አሟሟታቸው እንደዚህ ብለዋል ። "እድሳ ያልጨረሰው ቀኛዝማች ታፈሰ እንኳን በውና የውድማ ዝሆን ሲፎክር ድምጡን ሲሰማ ይጨ ነቅ የነበረው ተኵሶ ሲጥል በጕራዴ ሲመታ ፣ ከሁለተኛው ስልፍ ስማዕታ ከሚባለው አገር ሲደርስ ከንዱን ቆሰለ ። በቆሰለም ጊዜ እ ከሮቹ እንግዲህ ከጥሩ ሥር እናሳርፍህ አሉት ። እርሱ ግን ለኢጣልያ ወታደር እንዱ እጁ ይበቃል ብሎ ሲያባርር ከዚያ ላይ ወደቀ. . ."

1 Assedio di Macallè . . . P.260.



በማለት ጽፈውላቸዋል[1] ።

በዚህ ዓይነት ቀኛዝማች ታፈሰ አባይነህ ተዋግተው የሞቱት ፣ በረዓዮ ተራራ በግይ አጋምና በሰማዕታ በኩል ከዘመተው ከጀኔራል አሪሞንዲና ከተጠባባቂው ከጀኔራል ኤሌና ጦር ጋር በተደረገው ውጊያ ላይ ነው ። ተመትተው የወደቁትም ከሰማዕታ ጕብታ አጠገብ መሆኑ ነው ። ቀኛዝማች ታፈሰ ዓባይነህ የልዑል ራስ እምሩ አጐት ያባታቸው የደጃች ኃይለ ሥላሴ ታናሽ ወንድም ናቸው ።

ረ/ ፊታውራሪ ዳምጠው ፣ የፈረስ ስማቸው አባ ሸንው የራስ ደስታና የማገርር ጄኔራል አበበ ዳምጠው አባት ናቸው ። በ1881 ዓ.ም. እንፊታውራሪ ገበየሁ ሽቃ እየተባሉ ሰናድር ያዥን ሲያዙ ፣ እርሳቸው ባላምባራስ ተብለው የፈረሰኛ ዘበኛ አሊቃ ነበሩ ። በኋላ የፊታውራሪነት ማዕረግ አግኝተዋል ።

እንደ ጸሐፊ ትእዛዝ አጻጻፍ ፣ ፊታውራሪ ዳምጠው ሲዋጉ የሞቱት በዚሁ ቀኛዝማች ታፈሰ በሞቱበት የጦር ግንባር በሰማዕታ ጕብታ ይመስላል ። ተዋግተው የሞቱትም ከመስኩብ በተመለሱ በዐሥረኛው ወር ምንም የዕረፍት ጊዜ ሳያገኙ በዙረት ላይ እንዳሉ ማለት ነው ።

በተረፈ ከነዚሀ በቀር በዓድዋ ጦርነት ሕይወታቸውን የሠዉት ከየመጽሐፉ የተሰቀሙት ቀጥለው ያሉት ናቸው ።

፩/ ደጃች ግን እየ የፈረስ ስማቸው አባ ባሕር ፣ ቀድሞ የደጃች አመንሸዋ የጦር አዛዥ ነበሩ ። ደጃች አመንሸዋ ሲሞቱና ጦራቸው ለራስ መኰንን ሲሰጥ ፣ እርሳቸውም ወደ ራስ መኰንን ዞረው ባፄ ምኒልክ ፈቃድ ደጃዝማች ተብለው ጨርጨርን ይገዙ ነበር ።[2]

፪/ ፊታውራሪ ወልደ ሚካኤል የሚታው ባላባት የፊታውራሪ ገረሙ ልጅ ፣

፫/ ቀኛዝማች አባይነህ የቀኛዝማች ታፈሰና የደጃዝማች ኃይለ ሥላሴ አባት ፣

፬/ ቀኛዝማች ተገኘ ወርቅ የንጉሥ ተክለ ሃይማኖት የታወቀ ጀግና ፣

1 ታሪክ ዘመን ዘዳግማዊ ምኒልክ ፣ ገጽ 267 ።
2 ዋ በለው ፣ ብላቴን ጌታ ማኅተመ ሥላሴ ፣ ገጽ 18 ።

፬/ ፊታውራሪ እምባቆ ከዓድዋ በፊት በማይ መሬት ጦርነት የሞቱ፣
፭/ ቀኛዝማች ተሰማ ወልዴ፣
፮/ ፊታውራሪ ጀንኩሩ የደጃች በሻህ ጭፍራ፣
፯/ ባላምባራስ በለው፣
፰/ " እደራ፣
፱/ " ሰይፉ፣
፲፩/ አቶ መላኩ የፈረስ ዘበኛ።

የካቲት 23 ቀን ከማለዳ ጀምሮ እስከ እኩለ ሌሊት በቆየው በዚህ ጦርነት የሞቱት ብዙዎች መሆናቸው ግልጽ ነው። በንጉሥ ተክለ ሃይማኖት፣ በየራሶቹና በየደጃዝማቾቹ ውስጥ ሆኖ ዘምቶ የሞተውና የቆሰለው ብዙ መሆኑ ሲታወቅ ከሰነድ ጥቂት የተገኘ፣ ስማቸውን በዚህ የታሪክ መጽሐፍ ላይ ለማግኘት አለመቻሉ ያሳዝናል።

ከዚህ ጋር ደግሞ፣ ካፒቴን ክሎቬት የሚባል የፈረንሳይ ተወላጅ በበጅሮንድ ባልቻ ውስጥ ሆኖ በመድፍ ኢጣልያኖችን በመውጋት ኢትዮጵያን የዓድዋለት ማገልገሉን ልናስታውስ ይገባል። እርሱም በፈረንሣይ ጦር ሠራዊት ውስጥ በመድፈኛ ክፍል ሳለ፣ ዳ፤ ምኒልክ ዝብቶ በጦር ትምህርትና በሌላውም በብዙ ወታደር ነክ ጉዳይ ሲመክርና ሲያገለግል የቆየ ነው። በጦርነቱ ዋዜማ ዓመቱን ሁሉ ወታደሩን የጠመንጃና የመድፍ አተኳኮስ ሲያስተምር ነበረ ይባላል። በኋላም ጦርነቱን ለመካፈል አልጋውን ከሚጠብቁት ከራስ ዳርጌ ተሰናብቶ ከአዲስ አበባ ወደ ጦሩ ግንባር መጥቶ የካቲት 22 ቀን ደረሰ። በማግሥቱ ሲዋጋ ውሎ ከድሉ በኋላ በተራው እንደ አንድ ኢትዮጵያዊ መኰንን ባ፤ ምኒልክ ፊት ሲፎክር የተማረኩት ኢጣልያኖች አይተውታል።

ጆቫኒ ቴዶኔ የሚባለው ምርኮኛ የጦር መኰንን በጻፈው ውስጥ ስለ ካፒቴን ክሎቬት እንደዚህ ይላል። "... በ6 ሰዓት በንጉሡ ድንኳን ፊት እኛ እስረኞቹ ስናልፍ፣ ከንጉሠ ነገሥቱ ድንኳን በራፍ ላይ አንዱን አማርኛ የተቀመጠ ጠጕሩ ወርቅማ (ብሎንድ) ... እኛን በንቀት እያየ የሚስቅ ነጭ አየሁ።..."[1] ብሏል።

በተረፈ በዓድዋ የወደቀውና የቆሰለው የኢትዮጵያ ወታደር ከነመኳንንቱ ቁጥሩ በትክክል አይታወቅም። ግራዝማች የሴፍ አዲስ

1. I Ricordi di un Prigioniero, G. Tedone, P. 44; IL Generale Salsa: E. Canevari P. 97.



አበባ ላሉት ለሙሴ ሞንዶን ሲያስተላልፉ፣ የሞቱትን ቁጥር 3867 አድርገውታል። እንኮንቲ ሮሲኒ ከብዙ የኢጣልያ መጽሐፎችና ከቃል ጥያቄ ለቅመው የሞቱትን ቁጥር ከ5 እስከ 7 ሺ ከፍ ሲያደርጉት፣ ጉግሾ ከ7 እስከ 10 ሺ አድርሰውታል። የቆሰለኞውንም ልክ ወደ ሺቸው ቁጥር የሚያደርሱት አሉ። ሚስተር በርክሌ የሚባሉት እንግሊዛዊ የሟቾቹን ኢትዮጵያውያን ቁጥር 7ሺ፣ የቆሰለኞውን ቁጥር 10 ሺ አድርሰውታል።[1]

ንጉሠ ነገሥቱ፣ ከመሳፍንቱ፣ ከመኳንንቱና ከሠራዊቱ ጋር ወደ ሰፈራቸው ከተመለሱ በኋላ በተገኘው ድል ምንም እንኳን ደስታ፣ ቢደረግ ስለሞቱትና ስለቆሰሉት በደስታው ጐን ሐዘን፣ ጭንቀትና ለቅሶ፣ እንደ ተደረገ የታወቀ ነው። በማናቸውም ድል አድራጊ አገር እንደ ሚደርሰው የንጉሠ ነገሥቱም የሁሉም ደስታ በሐዘን የተበረዘ ነው ማለት ይቻላል። ወደ ሰፈር መልስ ከሆነ በኋላ፣ ከማግሥቱ ጀምሮ ንጉሠ ነገሥቱ በያለበት የወደቁትን የኢትዮጵያውያኑን ሬሣ እያስለቀሙ ሲያስቀብሩ፣ ቆስሉ የወደቀውን ወይም በቃሬዛ ከየክፍሉ ጦሩ የመጣውን ሁሉ በመድኃኒት ሲያሳክሙ፣ በየመንደሩም እያሳደሩ ሲያስታምሙ፣ በየጦሩ ጕራ በየአለበት የተበታተነውን የጠላት መድፍና ጠመንጃ፣ ጥይትና ቀለህ ሲያሰበስቡ ሰነበቱ። ከንጉሠ ነገሥቱና ከእቴጌይቱ ጀምሮ ሁሉም በዕብሪተኛው ጠላት ላይ በተገኘው ድል የተደሰተ ቢሆንም ከታወቁት አርበኞች ከነገበየሁ፣ ከነታፈሰ ጋር በጠቅላላው ቁጥራቸው እስከ 7 ሺ የሚደርስ ከመኳንንት፣ ከሹማምንትና ከተራ ወታደርም ስለሞተው ወገን፣ ሁሉም ማዘኑ የታወቀ ነው።

ይህን አስመልክተው ጸሐፊ ትእዛዝ ገብረ ሥላሴ፣ "ከሰልፍ ላይ ስለቀሩት እጅግ አጥብቆ ሐዘን ሆነ" ካሉ በኋላ፣ አልፍ ብለው "ንግሥቲቱ እቴጌ ጣይቱ ስለ አሽከሮቻቸው፣ ስለ ወዳጆቻቸው፣ ስለ ክርስቲያኑ ማለቅ መራራ ሐዘን አዘኑ። ብርሃን የመሰለ ፊታቸው እተላስ (ጥላት) እስኪመስል አለቀሱ ... ነገር ግን፣ እንደ ተነሡ ብዛት፣ እንደቀትነ ርዝመት፣ ሰው ሞተ ብሉ ያዘነ የለም። ባሏም፣ ልጅዋም፣ ወንድሟም የሞተው እንኳን አልጋው ቆመልን ነው እንጂ፣ ባሌ ልጄ ወንድሜ ሞተብኝ ብሉ ያዘነ የለም"[2] ሲሉ ገልጸውታል። ያዘነ የለም ማለታቸው ያነጋገር ፈሊጥ ወይም ከሐዘኑ የተገኘው ድል መብለጡን ለማመልከት ነው እንጂ፣ ሐዘኑማ ሐዘን መሆኑ አይቀርም። በሐዘኑ ላይ ግን፣ የድል አድራጊነትና የነጻነት ደስታ ተበርዞ ሐዘኑን አቀዝቅዞታል ማለት ነው። እነዚህ ሁሉ አልቀው ድሉ ባይገኝ ኖሮ ሐዘኑ ከመራራ ደረጃ ላይ ይደርስ ነበር።

1 Italia ed Etiopia ... P. 452, G.F.H. Berkeley PP. 346—347
2 ታሪክ ዘመን ዘዳግማዊ ምኒልክ—ገ.ሥ. ገጽ 257—268

# ምዕራፍ ዐርባ አምስት

## የኢጣሊያ ጦር መፍረስና ቅጥ ያጣ ሽሽት

ቅጥሩ ሐያ ፳ የሚያደርሰው ባንድ ሌተና ጄኔራልና ባራት ማጆር ጄኔራሎች የተመራውና ጦርነት የጠማው፣ ሰላም ያንገፈገፈው የኢጣልያ ጦር እንዠ ባፄ ምኒልክ የጦር ሠራዊት ተመትቶ ፍርስርሱ ወጣ። የሞተው ሞቶ የተረፈው ሸሸ። ከአልቤርቶኒ ጦር የተረፈው ወደ ሳውሪያ፣ ከዳቦርሚዳና ከአሪሞንዲ ጦር የተረፈው በቁሃና በመሬት ማይ በኩል አድርጎ ራቁን ወደ መረብ፣ ወደ አዲ ቀይሀ፣ ወደ አዲግራት፣ ወደ አሥመራ መሰሰ። በየበኩሉ ቅጥ ባጣ መንገድ እየተዝረከረከ በቁስል እየተሰቃየ፣ ረኃብና ጥም፣ እርዛትና ድካም እያንገፈገፈው እየ ወደቀና እየተንገዳገደ ከመንገድ ላይ ይገኛል።

ጣሊያኖቹ፣ ለድሉ በፍጹም እርግጠኞች ከመሆን የተነሣ፣ "ምናልባት የተሸነፍን እንደሆን እዚህ ቦታ ተገናኝተን በዚህ መሥመር እየተከታተልን ወደ መጣንበት እንመለሳለን" የሚል ከጠቅላይ አዛዡ የተሰጠ ምንም ዐይነት ፕላን አልነበረም። የጦርነቱ አመራር ራሱ ከፕላን ውጭ ሆኖ እንደ ተዘባረቀ የሸሸቱ ነገርም ከዚያ የበለጠ ተበላሽቶ ብዙ ወታደር በየፊናው ሲሔድ፣ የኢትዮጵያ ወታደር እየደረሰ በጥይትና በጐራዴ ሲያተራምሰው ባላገር በበኩሉ እየተቀበለ በዱላና በሽመል እየመታ የገደለው ብዙ ነበር።

ጄኔራል አልቤርቶኒ፣ በቅድሚያ ሲማረክ፣ ጄኔራል አሪሞንዲና ዳቦርሚዳ በጦርነቱ ሜዳ ላይ ሞተዋል። የተጠባባቂው ጦር አዛዥ ጄኔራል ኤሌናና ዋናው ጠቅላይ አዛዥ ጄኔራል ባራቲዬሪ ብቻ አምልጠው ወደ አዲ ቀይሀ አመሩ። እነርሱም በየጦሩ ሜዳ ድል አድራጊው ጦር እያዋከበ መምጣቱን ተመልክተው ለጊዜው ባጋጣሚ አጠገባቸው ከተገኙት ጋር ተመካከረው የጦርነቱን ፍጻሜ ሳያዩ፣ "ከመከበባችን በፊት እናምልጥ" ብለው ሸሹ። ጠቅላይ አዛዥ፣ የጄኔራል አልቤርቶኒን መማረክ፣ የሁለቱን ጄኔራሎች ማለትም የዳቦርሚዳንና የአሪሞንዲን መሞት አያውቅም ነበር። የራሳቸው የኢጣልያኖቹ የታሪክ ሰነድ እንደሚያመለክተው፣ አጦር ግንባር ከቀረበው 17,000 ወታደር ውስጥ ወደ አሥመራና ወደ አዲግራት ሸሽተው ነፍሳቸውን ያዳኑት

ሲል እንዲራመድ በዱላ ስንደበድበው ወደኋላ ተሰዶቶ እንዳይቀርም ባላገር እንደሚነድበው ስለሚያውቅ የጉዱን መራመድ ይጀምራል። እኛ ሹማምንቱ ወታደሮቻችን በጎድ እንዲራመዱ ለመደብደብ ጭካኔ አስፈለጎን ነበር።... እንደዚሁ ባንድ በታ ውለን ስንጓዝ ከሜካ ውስጥ ተተኩሶ አንድ ጓደኛችን ተመታ። ሊድን የማይችል መሆኑንም ስናውቅ ትንሽ ውሃ አጠገቡ ትተንለት ተለነው ሔድን። ባንድ ስፍራ ስንደርስ በፊት ለፊት እሳት በብዙ የሚነድ አየን። የጠላት ሰፈር መሆኑንም የሚመራን ያገር ተወላጅ ስለ ተናገረ እንብታ ላይ ወተተን መግሪያችንን ጠምደን ተኛን። ከዚያም በማግሥቱ የኛ ምቹ ወላንድ መንደር ገብተው ስንቅ ሲፈልጉ ከባላገሩ ጋር ተዋጉና ሦስቱ ሞቱ። እኛም በሩቅ እየተኮስን ባላገሮቹን ብዙ እየገደልን አባ ረርን። ቢሆንም እንደገና ጉዞ ጀምረን የምንጓዝበት ሜዳ ውሃ የሌለ በት ስለሆነ ውሀ ጥም እንደገና ያሰቃየን ጀመር። ወታደሩም እየተኛ ስላስቸገረን ተነሡና ተራመዱ ለማለት የኔም የራሴ ምላሴም ጉሮሮ ዬም በውሃ ጥም ተዘጋና መናገርም አቃተኝ።

የሆነ ሆኖ፣ ውሃ እፊታችን እቅርብ እለ እያልን እያባበልን እስከ ሥተን ሁሉም እያቃሰተና እያዛለ ይጓዝ ጀመር። ሲነጋ መጋቢት 5 ቀን (የካቲት 27 ቀን) አንድ የረጋ ውሃ አየንና እኔና ካፒቴን ተጅሩጠን ተዘርግተን በብዙ ጠጣን። ከጠጣንም በኋላ ከውሃው ጋር የግመል ሽንት እንዳለበት ተረዳን። ነገር ግን መቶ ሜትር እልፍ ስንል ሌላ መልካም ውሃ ተገኘና ሁሉም እንደልቡ ይጠጣ ጀመር.. በማግሥቱ ከሌሊት በ4(10) ሰዓት ጉዞው ቀጠለ። የውሃ ጥም እሰቃ የን። ለምናልፍበት መንገድ ለምልም ግር ስለነበረ ከርሱ እየነጩን እያኘክን እንደ እንስሳ ጉሮሯችን ውሀውን እንመጥ ነበር።...በመ ጨረሻ አንድ ውሀ የተጠራቀመበትን ስፍራ ሲነጋ ስላየን ሰውም ከብቱም ወደዚያ እየተሯሯጠ ሔዶ ጠጣ...ሔደን ሔደን ባንድ ሜዳ ላይ ስንደርስ የኢጣልያኖች ሬሳ እተረፈረፈበት ደርሰን ሁሉም ራቁ ቱን የሆነ ግማሹ በውነቱን የተቆራረጠ ነበረበት። በንደርስ እንጉ ከቶኛ ቆስሎ አልሞተ ነር ተነሥቶ የጦርነቱን ሁኔታ ትንሽ አነጋገ ረን... የነዚህን የገማኖቻችንን ሬሳ ለአሞራና ለጅብ ትተን በሐዘን እልፈናቸው ሔድን። ሴሎች ያልሞቱ ሁለት ጣልያኖች ራቁታቸውን ተነሥተው እየሮጡ ተከተሉን። ከሁለት እንዳቸው በጣም ለሞት የቀ ረበ መሆኑን ስለተረዳን ከውሃ አጠገብ ተለነው ሔድን። እንደኛው ግን ጉዞውን ከኛ ጋር ቀጠለ...የኛ ሰፈር ወደ ነበረበት እቅራቢያ ስንደርስ ደስ ብሎን ነበር። ዳሩ ግን ዐሥር ቁስለኛ ያስከተለ አንድ የ50 አለቃ (ሰርጀንት) አገኘንና ሰፈራችን ሁሉ በጠላት መያዙን ገለጸ ልን። የጦር ሠራዊታችን ሁሉ ወዴት ሔደ ብለን ብንጠይቀውም "የፈረሰ ይመስለኛል" ብሎ ወደኋላ እንደሚገኝ አስግቀን ስለነገረን እኛ ሹማምንቱ እርስ በርሳችን እየተያየን የጦራችንን መፍረስ ተገን ዘብን።

ከዚህ በኋላ ምን ይሻላል በፊታችንም በኋላችንም አበሾች አሉ። ስድሳ የምንሆነው የደከምነው ሰዎች ከዚሁ ሐያ ቁስለኛ ስምንቱ የጸናባቸው ሆነን ወደኋላ እንሔዳለን እየተባባልን ስንከራከር ቆይተን ወደ ሰሜን 300 ኪሎ ሜትር እንደገና ተጉዘን እሥመራ ከመድረስ በቀር ሌላ የደኅንነት መንገድ አለመኖሩን ብንረዳውም ይኸንን



በደከመ ጉልበት ያለበንት በጠላት አገር በተናደደና በሚዋጋን ባላ ገር መካከል አልፈን እንደምን እንደርሳለን ከተባባልን በኋላ በርቱ ተበረታቱ ልጆች ተባብለን ጉዞውን ጀመርን። ስንጓዝ ውለን በ6(12) ሰዓት አሁንም ጉዟችንን በንቀጥል ከወደፊታችን ሰዎች ሲመጡ አየ ንና ጠላቶቻችን መስለውን ለተኩስ ተሰናዳን። በዚያ ጊዜ አንድ ወታደር "የጦር መኰንን ነው" ብሎ (በኢጣልያ ቋንቋ) ስለጮኸ መተኮሳችንን ትተን ብንመለከት፣ በውነትም የጠፉትን ወታደሮች ለመፈለግ ሲል ባላገርና ወታደር አስከትሎ የሚመጣ የእግሊዮ ባታ የጦር መኰንን መሆኑን ተገንዝበን ተያይተን ስንገናኝ እርስ በርሳችን እንዳቀስ ጀመር። ከዚያ እነሱን አግኝተን በነርሱ እየተመራን የደከ ምን የቆሰልን ብንሆንም፣ እንዳንማረክብን ብረታችንን በትከሻችን እንደ ያዝን ከ6 ቀን ጉዞ በኋላ ቁስለኞቻችንን ሳንተው (እሥመራ) ደረስንና ቅልጥማችን እየተንቀጠቀጠ በዚያ ለነበረው ለማዦር እግሊዮ የብ ረት ሰላምታ አቀረብንለት። በዚያ ያሉት ነጮችም ተቁርቾም እየተደ ነቁ እያዩን ሹማምንቱም በለያችን በናፍቆት እየወደቁ ሳሙን። ከዚያ ደገበኛ ዕረፍት አደረግን። እንደ ሕልምና ተረት የመሰለንን የኛንም መብል (ሚኒስትሮኒ) አቀረቡልን...

ሲል የጦር መኰንኑ የሸሹትን ሁኔታ በዚህ ዓይነት ዘርዝሮ ይደመድ ማል[1]።

ድንገተኛ አደጋ በመጣል የኢትዮጵያን ነጻነት ደምስሰው አገሪ ቱን ለመውረር፣ እንዲሁም በአላጌና በመቀሌ የደረሰባቸውን የወታደ ርነት ውርደት ለማደስና የኢጣልያን መንግሥትና ሕዝብ መንፈስ በኩራት እንመላሳለን ብለው የመጡት፣ የኢጣልያ የጦር መኰንኖችና ወታደሮች እነሆ እጦርነቱ ላይ የሞቱት የአሞራና የጅብ ራት ሲሆኑ፣ ጥቂቶቹ በኢትዮጵያ የጦር ሠራዊት ተማረኩ። የቀሩት ደግሞ ተዝ ረክርከው ወደ መጡበት ተመለሱ። ይህ ሁሉ ከመድረሱ በፊት ዐፄ ምኒልክና የወንድም አገልጋያቸው ራስ መኰንን እርቅ ሆኖ በሰላም እንዲመለሱ ምን ያህል ጣልያኖቹን እንደ ለመኑዋቸው ከዋናው ከዓድዋ ጦርነት በፊት ባሉት ምዕራፎች በሰፊው ተገልጿል።

እውነት ነው፣ ጠላትን በማናቸውም ረገድ ለማጥቃት ሲሞክር ሞራል፣ ይሉኝታና ሐቀኝነት እንዳይገባበት ኒኮላ ማኪያቬሊ የሚባ ለው የነርሱው ተወላጅ በፍልስፍና መንገድ አስተምሯል። ሐቀኝነት የማይወዱ የመንግሥታት መሪዎችም ሠርተውበታል። ዐፄ ምኒልክም የባራቲዬሪን ጦር ከምሽግ እንዲወጣ ያደረጉት በተንኮል መሆኑን አን ዘነጋም። ቢሆንም ሌሎቹ ለክዳታቸው ወይም ለተንኮላቸው ይሉኝታ

1 Lettere e Diari ... PP. 92-99.

## ምዕራፍ ዐርባ ስድስት

ሌተና ጄኔራል አንተኒዮ ባልዲሥራ አዲስ ጦር ይዞ ምጥዋ እንደገባ— ማጆር ቶማሶ ሳልሳ ስለ ዕርቅ ጉዳይ ወደ ምኒልክ እንደመጣ —ሌተና ሮሸርስ ባይት የተመለከተው የኢትዮጵያ ሠፈር—የዕርቁ ለጊዜው አለመሳካት

ከንጉሡ ጀምሮ እስከ መሳፍንቱ ፥ ከጠቅላይ ሚኒስትሩ ጀምሮ እስከ ተራው ሠራተኛ ፥ ከመከላከያ ሚኒስትሩ እንሥቶ እስከ ተራው ወታደር ድረስ የነበሩት ኢጣልያኖች ፥ ኢትዮጵያ በዚህ በምኒልክ አገዛዝ ወቅት የነበራትን ጠንካራ የውስጥ ሁኔታ ባለማወቅ ወይም በሙቅ በመናቅ በኢትዮጵያ ላይ የነበራቸው የመስፋፋት ምኞት ከፍ ያለ እንደነበር ተመልክተናል ። ዐፄ ምኒልክም ያን ያህል የሰላምና የእርቅ ነገር ደግመው ፥ ደጋግመው የፈተኑት ምንም የተደራጀ ጦር እንዳላቸው ቢያውቁም ፥ "እንሸነፍ ይሆን? በብዙ ድካም የተገነባው መንግሥታችን ፥ ብሔራዊ ግዛታችን መልሶ ይፈርስና ውርደት ያስከትልብን ይሆን" በሚል ሥጋት ውስጥ እንደነበሩ አይጠረጠርም ። ብዙ ጊዜ እንዳልነው ፥ ራስ መኰንን ኢጣልያን የጐበኙ ጊዜ የመንግሥቱ መሪዎች ሆን ብለው የወታደርና የመሣሪያ ድርጅታቸውን በጥንቃቄና በዝርዝር አሳይተው መልሰዋቸዋል ። ይህም ለጦርነቱ መጣተው ንጉሡንም እንዲያሥጋ በማመን ያደረጉት ይመስላል ። ጦርነቱ የተካሔደው በአንድ በኩል ለድል አድራጊነቱ ባልተጠራጠረ ፥ እሸናፊነቱን በተማመነ ፥ ራሱን ከፍ አድርጎ በኩራትና በትዕቢት ተወጥሮ የቅኝ ግዛት እምርት ባሰከረውና በሌላው ወገን ራሱን በትሕትና ዝቅ አድርጎ ለድል አድራጊነቱ በሥጋና በግድ የእናት አገሩን ነጻነት ለመከላከል ብቻ ለውጊያ በቆረጠ ሕዝብ መካከል ነው ። ዳግማዊ ምኒልክ ፥ በኩራትና በትምክህት ተመልቶ እስከ አሳጌ ድረስ በግሥጋሤ የመጣውን ኃይለኛ የጠላት ጦር ፥ በሰላም እምቢ ያለውን በውጊያ እየጠረጉ እስከ ዓድዋ ዘልቀው በሰፈሩበት ሰዓት ፥ የኢጣልያ መንግሥት በባራቲዬሪ አማካይነት ፥ ዝናን ፥ የወታደር ክብርን የሚያድስ ፥ ሰፋ ያለ ግዛት የሚያወርስ ድል በጉጉት ተጠብቆ ድሉ የወግኜታ ሆኖ ቀረ ። ከዓድዋ ጦርነት ጥቂት ጊዜ ቀደም ብሎ በሮማ ምክር ቤት በጥንቃቄ ምክር ተደርጎ በኢጣልያ የጦር ሠራዊት ውስጥ

፲፫ኛ  የኢጣልያ ጦር በዓድዋ ሲፈርስ በአዲግራት ምሽግ እንደ ተከበቡ የተቀመጡትን ጣሊያኖች በስምምነት ማስለቀቅ፣

፲፬ኛ  በከሰላ በኩልም ኢጣልያኖች በደርቡሾች ተከበዋል የሚል ወሬ ስለተሰማ ለነርሱም እርዳታ መላክ ።

ስለዚህ፣ በሌሎቹ ቁጥሮች የተመለከቱትን ጉዳዮች በትጋት ከማ ከናወን ጋር በ፲፫ኛና በ፲፬ኛ ቁጥሮች የተመለከቱትን ጉዳዮች ለመፈ ጸም፣ ከጦርነቱ በፊት ወዳጄ ምኒልክ ዘንድ በመላክ የታወቀው ማጆር ቶማሶ ሳልሳ ተመረጠ ። ለርሱም ረዳት የሚሆነው የኢትዮጵያውያንን ባህልና የትግርኛ ቋንቋ የሚያውቀው የአዲኳላ ምስለኔ ቴኔንቴ ሮዠርሲ ተጨመረለት ። ከነዚህም ጋር ከብዙ ጊዜ ጀምሮ ባስተርጓሚነት በኢጣልያኖች ዘንድ የታወቁት፣ ደጃች ባሕታ ከኢጣልያ ሸፍተው የሰገነይቲውን ምስለኔ ቴኔንቴ ሳንጉይኔቲን ያሰሩ ጊዜ ስለ ኢጣልያኖቹ መኰንን አስራትና መጉላላት ከባሕታ ሐጐስ ጋር የተጣሉትና በዚህም ሥራቸው ሁሉ በኢጣልያኖች ዘንድ በጣም የተ ወደዱት አቶ ገብረ እግዚአብሔር ተሰጡት ።

በዚህ ዐይነት ማጆር ሳልሳ እነዚህን እንዳስከተለ በሐያ ሰው ታጅቦ ከአሥመራ ወደ አዲኳላ መጣ ። ከገኔራል ባልዲሠራ እንደ ታዘ ዘው የአዲኳላ ምስለኔ ስለ ሰላም እንዲዋዋል የኢጣልያ መንግሥት ማጆር ቶማሶ ሳልሳን መሾሙን ዐፄ ምኒልክ ዐውቀው እንዲቀበሉት ለራስ መኰንን ደብዳቤ በመላክተኛ እጅ በቶሎ ላከ ። አዲኳላ ሆነው ሌቱንም ምንም እንቅልፍ ሳይወስዳቸው ሲጠብቁ አድረው መልስ ስላልመጣ፣ መሄም መፈቀዱ አይቀርም ብለው ጉዟቸውን ወደፊት ቀጥለው በየካቲት 27 ቀን (መጋቢት 6 ቀን) ጉንደትን አልፍ እንዳሉ ከራስ መኰንን ዘንድ ከተላኩት መላክተኞች ጋር በመንገድ ተገናኙና ከራስ መኰንን የተጻፈውን ደብዳቤ ለሳልሳ ሰጡት ። በደብዳቤው ላይ ንጉሠ ነገሥቱ ሳልሳን ለመቀበል መፍቀዳቸው፣ እነርሱንም እየመሩ የሚወስዱ ሁለት መኳንንት ታዘው መንገድ መጀመራቸው ተገለጸለት ።

በዚህ ዐይነት ተጉዘው አዲ ቀሆት ሲደርሱ፣ ከሁለቱ መኳንንት ጋር ተገናኙ ። እነርሱም ፊታውራሪ ደሳለኝ የራስ መኰንን መላክተኛ፣ ደጃች አርአያ የራስ መንገሻ ዮሐንስ መላክተኛ ናቸው ። ከእነርሱም ጋር በመልካም መግባባትና ሰላምታ ከተገናኙ በኋላ፣ አዲቀሆት የደጃች አርአያ ግዛት ስለሆነ፣ በመልካም መስተንግዶ አድረው በማግ ሥቱ ከመጋቢት 11 እ.ኤ.አ. ጀምሮ ተጉዘው ዐፄ ምኒልክ ሰፈር እስኪደርሱ ድረስ ያዩትን ሁኔታ በቀጥታ ከራሱ ከቴኔንቴ ሮዠርሲ ጽሑፍ መመልከት የተሻለ ነው ።



...ከአዲ ቀሆት በማግሥቱ ተነሥተን 3 ሰዓት እንደ ተጓዝን ዐፄ ምኒልክ ያሉበትን እኛም መኳንንቱም አናውቅም ነበርና እስተ ዋቴ ፊታውራሪ ደሳለኝ በያዘው መንደር እተከተር ሲያይ እንደ ደመና የቆመ አቧራ ተመለከተና ወደ ፊረስ ማይ የሚጓዘው የሸዋ ጦር (ዐፄ ምኒልክ) ነው ብሎ ነገረን ። ወደዚያም ለመድረስ የቱንን ሜዳ ማቋረጥ ነበረብን ። በዚሁ ሜዳ በመጋቢት 1 ቀን (የካቲት 23) የሞቱት ያብዛኞች ጣልያኖች ሬሳ ፊታቸውን ወደ አንዲት ፈሳሽ ወንዝ አድርገው እንደወደቁ ይታዩ ነበር ። ሜዳው በሙሉ በሬሳ ተሸፍኖ ነበር ። በአፍሪካ 6 ዓመት ስኖር ብዙ ቁስለኛና ሬሳ አይቻ ለው፣ የአቆርደትንም የጦር ሜዳ ተመልክቻለሁ ። ነገር ግን በዚህ ቀን በዓድዋ ሜዳ እንዳየሁት የመሰለ የሬሳ ብዛት በፍጹም አይቼ አላ ውቅም ። ጦርነቱ በተደረገ በ፰ኛው ቀን በመካከሉ ሳልፍ ሬሳውን አሞራዎች ሳይነኩት ጅብም ሳይነካው እንዳለ ነበር ... ሬሳው አንዱ ካንዱ የተቀላቀለ በመሆኑ በቅሎዎችን በእግራቸው እንዳይረግጡት በጥንቃቄ እንመራቸው ነበር ። ... በሬሳ የተሸፈነው ረጅሙ ሜዳ እስተ ድረስ በመሐረቤ አፍንጫዬን ይዤ ዐይኖቼን ጨፍግፌ ከድኜ አቋረጥኩ ።

የማጆር ሳልሳ ተከታይ ሆኖ የተላከው ሌተና ሮዠርሲ፣ የጉዞ
ን አስቀያሚና አሠቃቂ ሥዕል በዚህ ዓይነት ካመለከተ በኋላ
ፄ ምኒልክ ከዓድዋ ወደ እንትጮ ተዛውረው እስቡበት እዳራሽ ገብቶ
ውን ሁኔታ ደግሞ እንደዚህ ሲል በመተረክ ያቀርባል ።

...ምኒልክ በዙሪያቸው ያሉ ልብስ የለበሱ መኳንንቶች አስከት ለው ከዓድዋ መጥተው እንትጮው እንደ ደረሱ ሰፈር አደረጉ ። ከሰዓት በኋላም እቴጌ ጣይቱ ደረሱ ። በብዙ ሺ የሚቆጠሩ መጠናቸው የተለያየ ነጫጭ ድንኳኖች በትንሽ ደቂቃዎች ውስጥ ተተክለው አየናቸው ። የጅማምንቱ ድንኳኖች ልዩ ልዩ ቀለም ነበራቸው ። ሰፈሩ በሥነ ሥርዓትና ፍጥነት ባለው ጊዜ ውስጥ ተሠርቶ አልቆ ሳየው እስካሁን ድረስ በዐይኔ ፊት የሚታየኝ ያማረ ሥዕል ሆኖ ይታ የኛል ። በ4 (10) ሰዓት አንድ የራስ መኰንን ወታደር መጥቶ ወደ ጌታው ወሰደን ። ከርሱም አንዱ ሹም ተቀብሎ ከራስ መኰንን ድንኳን ሁለት መቶ ሜትር ርቆ የተዘጋጀልንን ድንኳን አሳረፈን ። ከማታው በ፰ ሰዓት (2) ራስ መኰንን ወደ ድንኳናቸው ጠርተውን ተገናኘንና መጠጥ ጋበዙን ። ከዚያ ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ነገ ትገናኛ ላችሁ ብለው አሰናበቱን ። ከደረስንበት ጊዜ ጀምሮ ጧትና ማታ ምግ ባቸውን በደንብ ይመላለስልን ነበር ።

በማግሥቱ ጧት፣ ፊታውራሪ ደሳለኝ መጥቶ እየመራ ወደ ንጉሡ ወሰደን ። 500 ሜትር ርቀት ባለው በንጉሠ ነገሥቱ ድንኳን ዙሪያ ያልታወቀ ሰው እንዳይገባ ጨዋትና ልፍለፋ እንዳይደረግ ወታደሩ እንደ አጥር ሆኖ ይጠባበቃል ። ከዚህ የወታደር አጥር ላይ ስንደርስ የጭን ከብቶቻችንንና ተከታዮቻችንን ትተን እንድንገባ ተገደድን ። ወዳንድ ልዩ ድንኳን ገብተን ዐርፈን እንደቆየን አንድ ሰው መጣና ማጆር ሳልሳን ጠራው ። መሣሪያ አለመያዙን ለማረጋገጥ እየበረበረ ከፈተሸው በኋላ ወዳጄ ምኒልክ ይዞት ሔደ ። እኩል ሰዓት ከቆየ በኋላ

፱ኛ የኢጣልያ ጦር በዓድዋ ሲፈርስ በአዲግራት ምሽግ እንደ ተከበቡ የተቀመጡትን ጣሊያኖች በስምምነት ማስለቀቅ፣

፲ኛ በከሰላ በኩልም ኢጣልያኖች በደርቡሾች ተከበዋል የሚሉ ወሬ ስለተሰማ ለነርሱም እርዳታ መላክ ።

ስለዚህ፣ በሌሎቹ ቁጥሮች የተመለከቱትን ጉዳዮች በትጋት ከግ ከናወን ጋር በ፲ኛና በ፱ኛ ቁጥሮች የተመለከቱትን ጉዳዮች ለመፈጸም፣ ከጦርነቱ በፊት ወዳፄ ምኒልክ ዘንድ በመላክ የታወቀው ማጆር ቶማሶ ሳልሳ ተመረጠ ። ለርሱም ረዳት የሚሆነው የኢትዮጵያውያንን ባህልና የትግርኛ ቋንቋ የሚያውቀው የአዲኳላ ምስለኔ ቲኔንቴ ሮቬርሲ ተጨመረለት ። ከነዚህም ጋር ከብዙ ጊዜ ጀምሮ ባስተርጓሚነት በኢጣልያኖች ዘንድ የታወቁት፣ ደጃች ባሕታ ከኢጣልያ ሸፍተው የስተንይቴውን ምስለኔ ቲኔንቴ ሳንጉይኔቲን ያሰሩ ጊዜ ስለ ኢጣልያዊው መኰንን እሰራትና መንገላታት ከባሕታ ሐጎስ ጋር የተጣሉትና በዚህም ሥራቸው ሁሉ በኢጣልያኖች ዘንድ በጣም የተወደዱት አቶ ገብረ እግዚአብሔር ተሰጡት ።

በዚህ ዐይነት ማጆር ሳልሳ እነዚህን እንዳስከተለ በሐያ ሰው ታጅቦ ከአሥመራ ወደ አዲኳላ መጣ ። ከጀኔራል ባልዲሠራ እንደ ታዘዘው የአዲኳላ ምስለኔ ስለ ሰላም እንዲዋዋል የኢጣልያ መንግሥት ማጆር ቶማሶ ሳልሳን መሾሙን ዐፄ ምኒልክ ዐውቀው እንዲቀበሉት ለራስ መኰንን ደብዳቤ በመላክተኛ እጅ በቶሎ ላከ ። አዲኳላ ሆነው ሌሊቱንም ምንም እንቅልፍ ሳይወስዳቸው ሲጠብቁ አድረው መልስ ስላልመጣ፣ መሄድም መፈቀዱ አይቀርም ብለው ጉዟቸውን ወደፊት ቀጥለው በየካቲት 27 ቀን (መጋቢት 6 ቀን) ጉንደትን አለፍ እንዳሉ ከራስ መኰንን ዘንድ ከተላኩት መላክተኞች ጋር በመንገድ ተገናኙና ከራስ መኰንን የተጻፈውን ደብዳቤ ለሳልሳ ሰጡት ። በደብዳቤው ላይ ንጉሠ ነገሥቱ ሳልሳን ለመቀበል መፍቀዳቸው፣ እነርሱንም እየመሩ የሚወስዱ ሁለት መኳንንት ታዘው መንገድ መጀመራቸው ተገለጸለት ።

በዚህ ዐይነት ተጉዘው አዲ ቀሆት ሲደርሱ፣ ከሁለቱ መኳንንት ጋር ተገናኙ ። እነርሱም ፊታውራሪ ደሳለኝ የራስ መኰንን መላክተኛ፣ ደጃች አርአያ የራስ መንገሻ ዮሐንስ መላክተኛ ናቸው ። ከእነርሱም ጋር በመልካም መግባባትና ስምምነት ከተገናኙ በኋላ፣ አዲቀሆት የደጃች አርአያ ግዛት ስለሆነ፣ በመልካም መስተንግዶ አድረው በማግሥቱ ከመጋቢት 11 እ.ኤ.አ. ጀምሮ ተጉዘው ዐፄ ምኒልክ ሰፈር እስኪደርሱ ድረስ ያዩትን ሁኔታ በቀጥታ ከራሱ ከቲኔንቴ ሮቬርሲ ጽሑፍ መመልከት የተሻለ ነው ።



...ከአዲ ቀሆት በማግሥቱ ተነሥተን 3 ሰዓት እንደ ተጓዝን ዐፄ ምኒልክ ያሉበትን እኛም መኳንንቱም አናውቅም ነበርና አስተዋዩ ፊታውራሪ ደሳለኝ በያዘው መንገድ እተከተል ሲያይ እንደ ደመና የቆመ አቧራ ተመለከተና ወደ ፊረስ ማይ የሚጓዘው የሸዋ ጦር (ዐፄ ምኒልክ) ነው ብሎ ነገረን ። ወደዚያም ለመድረስ የሁለት ቀን ጉዞ ማድረግ ነበረብን ። በዚሁ ጉዞ በመጋቢት 1 ቀን (የካቲት 23) የሞቱት ያብቴዎች ጣልያኖች ፊላ ፊታቸውን ወደ እንዲት ፊላሽ ወንዝ አድርገው እንደወደቁ ይታዩ ነበር ። ጉዞው በሙሉ በሬሳ ተሸፍኖ ነበር ። በአፍሪካ 6 ዓመት ስኖር ብዙ ቁስለኛና ሬሳ አይቻለሁ፣ የአቅርዳትንም የጦር ጉዞ ተመልክቻለሁ ። ነገር ግን በዚህ ቀን በቅሃ ጉዞ እንዳየሁት የመሰለ የሬሳ ብዛት በፍጹም አይቼ አላውቅም ። ጦርነቱ በተደረገ በ8ኛው ቀን በመካከሉ ሳልፍ ሬሳውን አሞራዎቹ ሳይነኩት ጅብም ሳይነካው እንዳለ ነበር ... ሬሳው እንዲ ካንዱ የተቀራረበ በመሆኑ በቅሎዎቻችን በእግራቸው እንዳይረግጡት በጥንቃቄ እንመራቸው ነበር ። ... በሬሳ የተሸፈነው ረጅሙ ጉዞ አለቀ ድረስ በመሐረቤ አፍንጫዬን ይዤ ዐይኖቼን ባጋማሽ ከድኜ አቋረጥሁ ።

የማጆር ሳልሳ ተከታይ ሆኖ የተላከው ሌተና ሮቬርሲ፣ የጉዞውን አስቀያሚና አሠቃቂ ሥዕል በዚህ ዓይነት ካመለከተ በኋላ ዐፄ ምኒልክ ከዓድዋ ወደ እንትጮ ተዛውረው አሉበት አዳራሽ ገብቶ ያየውን ሁኔታ ደግሞ እንደዚህ ሲል በመተረክ ያቀርባል ።

...ምኒልክ በዙፋናቸው ያጌጠ ልብስ የለበሱ መኳንንቶች አስከትለው ከዓድዋ መጥተው እንትጮው እንደ ደረሱ ሰፈር አደረጉ ። ከሰዓት በኋላም እቴጌ ጣይቱ ደረሱ ። በብዙ ሺ የሚቆጠሩ መጠናቸው የተለያየ ነጫጭ ድንኳኖች በትንንሽ ደቂቃዎች ውስጥ ተተክለው አየናቸው ። የሹማምንቱ ድንኳኖች ልዩ ልዩ ቀለም ነበሩዋቸው ። ሰፈሩ በሥነ ሥርዓትና ፍጥነት ባለው ጊዜ ውስጥ ተሠርቶ አልቆ ሳየው እስካሁን ድረስ በዐይኔ ፊት የሚደቀን ያማረ ሥዕል ሆኖ ይታየኛል ። ፬ (10) ሰዓት አንድ የራስ መኰንን ወታደር መጥቶ ወደ ጊታው ወሰደን ። ከርሱም አንዱ ሹም ተቀብሎ ከራስ መኰንን ድንኳን ሁለት መቶ ሜትር ርቆ የተዘጋጀልንን ድንኳን አስረከበን ። ከማታው ፪ ሰዓት (2) ራስ መኰንን ወደ ድንኳናቸው ጠርተውን ተገናኘንና መጠጥ ጋበዙን ። ከዚያ ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር ነገ ትገናኛላችሁ ብለው አሰናበቱን ። ከደረስንበት ጊዜ ጀምሮ ጧትና ማታ ምግባችን በደንብ ይመላለስልን ነበር ።

በማግሥቱ ጧት፣ ፊታውራሪ ደሳለኝ መጥቶ እየመራ ወደ ንጉሡ ወሰደን ። 500 ሜትር ርቀት ባለው በንጉሠ ነገሥቱ ድንኳን ዙሪያ ያልታወቀ ሰው እንዳይገባ ጩኸትና ልፍለፋ እንዳይደረግ ወታደሩ እንደ አጥር ሆኖ ይጠባበቃል ። ከዚህ የወታደር አጥር ላይ ስንደርስ የጭን ከብቶቻችንንና ተከታዮቻችንን ትተን እንድንገባ ተገደድን ። ወዳንድ ልዩ ድንኳን ገብተን ዐርፈን እንደቆየን አንድ ሰው መጣና ማጆር ሳልሳን ጠራው ። መሣሪያ አለመያዙን ለማረጋገጥ እየበረበረ ከፈተሸው በኋላ ወዳፄ ምኒልክ ይዞት ሔደ ። እኩል ሰዓት ከቆየ በኋላ

